# ጸሐፌ ትዕዛዝ
# አክሊሉ ሀብተወልድ

## መስከረም 10 ቀን 1967 ዓ.ም.
## ለመርማሪ ኮሚስዮን ያቀረቡት ጽሑፍ

# ጸሐፌ ትዕዛዝ
# አክሊሉ ሀብተወልድ

## መስከረም 10 ቀን 1967 ዓ.ም.
## ለመርማሪ ኮሚስዮን ያቀረቡት ጽሑፍ



አዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ ፕሬስ

# ማውጫ

## ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ
## መስከረም 10 ቀን 1967 ዓ.ም.
## ለመርማሪ ኮሚሲዎን ያቀረቡት ጽሑፍ

- ተዚህ ቀጥሎ የተጻፈው እስር ቤት በነበርኩ ጊዜ በቃል የማስታውሰውን ነው።
- ፋይልና አስፈላጊውን ሰነድ ሳላይ ስለሆነ ያመተ ምህረትና ወራት፣ የስም ይህን የመሰለ ቲኒኒሽ ስህተት ሊኖር ይችላል።
- በጠቅላላው ግን ታሪኩና ፋክቱ እውነተኛና በዶኩመንትም ፕሩፍ ሊሆን የሚችል ነው።

*ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ*

# 1. ትምህርት

ሀ/ መጋቢት 5 ቀን 1904 ተወለድኩ፤ ያማርኛ ትምህርቴን በራጉኤል ቤተ ክርስቲያን አጠናቀቅሁ።

ለ/ የውጭ አገር ትምህርት ምኒልክ ተማሪ ቤት ለሁለትና ለሦስት ዓመት ተተማርኩ በኋላ፤ እ.ኤ.አ. በ1925 ዓ.ም አለክሳንድርያ፣ ግብጽ በሚገኘው የፈረንሳይ ሊሴ ትምህርቴን እንድቀጥል ተላክሁ።

ሐ/ እዚያም እ.ኤ.አ. ተ1925—1931 ትምህርቴን አጠናቅቂ የፈረንሳይን ባካሎሪያ /ባሸልዩ/ ተቀበልኩ።

መ/ ተዚያም ፓሪስ ሶርቦን ዩኒቨርሲቲ ገብቼ የሕግ ትምህርት ጀመርኩ። ሶርቦን ዩኒቨርሲቲ ሕጉን ስማር *ኦት ኤቱድ* /Houte Étude Connerdiala/ እንዲሁም *ሲዩንስ ፖለቲክ* የሚባሉ ከፍተኛ ትምህርት ቤቶችም ገብቼ እማር ነበር።

በነዚሁም ትምህርቴን አጠናቅቂ እ.ኤ.አ. ከ1931—1936 ያገኘኋቸው ዲግሪዎች፦

- ሊሳንስ የሕግ /L.L.B. ወይም Licence en Droit/
- ዲፕሎም ዶ ዶክቶራ በፑብሊክ ሉው /Diplôme de Doctorat en Droit Public/
- በኢኮኖሚክስ የዶክቶራ ዲፕሎም /Diplôme de Doctorat en Economique/
- ሰርቲፊካ ዶቱድ ሱፒሪዩንስ ኮምርሲአል /Certificat d' Étude Supreriance Commercials/
- የፖለቲካ ሳይንስ ተማሪ ቤት የጨረስኩበትን ሰርቲፊካ

## 1.1 ትምህርቴን በምማርበት ጊዜያት ስለ አገራችን ያደረኩት የፖለቲካ እንቅስቃሴ

አለክሳንድርያ ሊሴ በነበርኩበት ጊዜያት የኮፕቲክ ፓትርያርክ አቡነ ዮሐንስ ኢትዮጵያን ጎብኝተው ነበር። አዲስ አበባንም በጎበኙበት ጊዜያት 60 /ስልሳ/ ልጆችን ላስተምር ብለው ጠይቀው፤ 60 ልጆች ይዘው

መጥተው ነበር። አገራቸው ተደረሱ በኋላ፣ «እኔ የጠየቅሁት ስድስት ልጆች ብቻ ነበር፣ እነሱ ግን ስልሣ ላኩልኝ» እያሉ አማረሩ። ተዚህም በኋላ ልጆቹ በምግብም፣ በልብስም ከባድ ጉዳት ላይ ወደቁ። ተማሪዎቹ ተካይሮ እነሱ ካሉበት፣ አሌክሳንደርያ እኛ ወዳለንበት ሦስት ልጆች ልከው፣ «ይኸው ራቁታችንን ነን፤ በምግብም በመጉዳት በከፊል በሽተኛ ሆንናልና በተቻላችሁ እርዱን»፣ አሉ። ሲሲ ተማሪ ቤት ያለነው አንድ ሃያ የምንሆነው ተማሪዎች ያለንን ትርፍ ልብስ ላክንላቸው። ወዲያውኑ ይህንን ሁኔታ ለግርማዊነታቸው (ያን ጊዜ እልጋ ወራሽና ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ነበሩ) በቴሌግራም አስረድቼ የሚያስፈልገው እንዲደረግ አሳሰብኩ።

የግብፅ መንግሥት በሙቀትና በረፍት /ቫካንስ/ ጊዜያት አለክሳንደርያ እየተዛወረ ስለሚሠራ፣ ያን ጊዜም ሁኔታው ይህ ስለነበረና መንግሥቱ አለክሳንደርያ ስለሚገኝ፣ ታንዱ ባልንጀራዬ መሸሻ ኃይሉ ጋር፣ አሁን የሕግ መወሰኛ አባል፣ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሄደን ተሚኒስትሩ ጋር እንዲያገናኙን ጠይቀን ተብዙ ክርክር በኋላ ተቀበሉን። እሱም እንዲጋጣሚ የመገናኛ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ተጠባባቂ ሚኒስትር፣ ሃይማኖቱም ኮፕት ነበር። ስሙን አሁን አላስታውሰውም። ሁኔታውን በዝርዝር አስረድተን፣ «ትችሉ እንደሁ ጤናቸው ተጠብቆ በሚገባ እስተምሩ፤ አትችሉም እንደሁ በሕይወታቸው እንዲመለሱ አድርጉ። ግን እንደዚሁ ዝም ብላችሁ እነኝህ ልጆች በጉዳትና በበሽታ ቢያልቁ፣ ወደፊት የኢትዮጵያ ቤተክርስቲያንና የኮፕት ቤተክርስቲያን ግንኙነታቸው አስጊና እማቋረጥ ደረጃ ስለመድረሱ፤ እኛ ያሁኑ ተማሪዎች፣ ወደፊትም በየደረጃው የኢትዮጵያ አስተዳዳሪዎች እንደመሆናችን እናረጋግጥልሀለን»፣ አልነው። እሱም በነገሩ ተነክቶ፣ «እኔ ነገ ካይሮ እሄዳለሁ፣ እናንተም ልጆቹንም ወደዚያው ፓትርያርክ ይዛችሁዋቸው እንድትመጡ። ግን ያላችሁት ውሸት የሆነ ጊዜያት ወዮላችሁ!» ብሉን፣ ቀጠሮ ሰጠን።

በቀጠሮው ሰዓት ሚኒስትሩ ተልጆቹ ጋር አገኘን። በኔ አስተርጓሚነት፣ ሚኒስትሩና ፓትርያርኩ በተገኙበት፣ ልጆቹ ችግራቸውን ሁሉ አስረዱ። ሚኒስትሩም በኔና በመሸሻ ኃይሉ አስተርጓሚነት ልዩ

ልዩ ጥያቄ አደረገላቸው። በጠቅላላው ሁኔታው አሳዛኝ መሆኑን ሚኒስትሩ እንዲረዳው የተቻለኝን ያህል አስረዳሁ። በመጨረሻም ሁኔታው እኔ በፊት እንዳልኩት መሆኑን ገባው። በዚህ ጊዜያት በግርማዊነታቸው ለንጉሥ ፋሩቅ አንድ ቴሌግራም እንደተላከ ተነገረው። ቴሌግራሙም፣ «የታመሙት ልጆች ሆስፒታል ገብተው እንዲታከሙ፣ ሌሎችም ታልተቻለ እንዲመለሱ»፣ የሚል ነበር። ተዚህም በኋላ ሚኒስትሩና ፓትርያርኩ እዚያው እኛው ፊት እየተመካከሩ ለልጆቹ፦

ሀ/ ምግብ በደንብ እንዲሆንላቸው፣

ለ/ የኪስ ገንዘብ በወር አስፈላጊው እንዲሰጣቸው፣

ሐ/ ልብስም ሁለት ሁለት ለያንዳንዳቸው እኛው ተገንዘብ ያገርው ጋር ገዝተን እንድንሄድ ስምምነት አደረግን።

በስምምነቱም መሠረት ተገንዘብ ያኸርውና ተልጆቹ ጋር ገበያ ሄደን፣ ለያንዳንዳቸው ሁለት ልብስ ገዝተን ሰጠን። /እንደማስታውሰው ልጆቹ የሚመርጡት ልብስ ዋጋው በጣም የወጣውን ስለሆነ ገንዘብ ያገርው ለቅሶ ለቅሶ ይለው ነበር።/ በዚህ አኳኋን ሁሉንም በደንብ ታደረኩ በኋላ ወደ እለክሳንደርያ ተመለስኩ። የተማሪ ቤታችን ድሬክተር፣ «አንተ ተማሪ ነህ፣ ፖለቲካ ውስጥ መግባት የለብህም፣ ካይሮ የምትሄድበት ገንዘብ አልሰጥህም» ብሎኝ፣ ነበር። የሄድኩትም ተባልንጀሮቼ ተማሪዎች የውጭ አገር ገንዘብ ተበድሬ ነበር።

ይህ ደህና ሁኔታ ለስድስት ወር ተቆየ በኋላ እንደገና ልጆቹ ችግር ላይ መውደቃቸውና እስጊ ሁኔታ ላይ መሆናቸውን ሳኩብን። ሁኔታውን ስናስመረምር እውነትም በሚያሳዝን ደረጃ ላይ ነበሩ። ወዲያውኑ ለጃንሆይ ቴሌግራም አደረኩና ጉዳዩን አስረዳሁ። እሳቸውም ኢየሩሳሌም ያለንን ቆንሲል አቶ ጳውሎስን አዝዘው ካይሮ መጥተው ልጆቹ ወደ አዲስ አበባ እንዲመለሱ አደረጉ።

ከተማሪዎቹ መካከል የማስታውሳቸው እነ ፈለቀ እርገቱ /አሁን ቀኛዝማች/፣ ዘውዴ ገብረሕይወት /አሁን ቢትወደድ/፣ ተፈራ ሰይፉ፣ ተፈራ ሸሹና ወልደማርያም ኃይሌ /አሁን ጄኔራል/ ይገኙበታል። የዚህን

ታሪክ አቶ መሸሻ ኃይሉና ጀኔራል ወልደማርያም ኃይሌ ደህና አድርገው ያውቁታል።

## 1.2 ሶርቦን ዩኒቨርሲቲ ትምህርቴን በማጠናቅቅበት ጊዜያት

**ሞሶሉኒ** ኢትዮጵያን ለመውረር በበለጠ ያበረታታው ተፈረንሳይ መንግሥት ጋር ያደረገው ስምምነት ነው። ፈረንሳይ በትራዲሽን የኢትዮጵያ ወዳጅና ደጋፊ ሆና ሲኖር ተብዙ ዘመን ጀምሮ ነው። ይኸውም በባቡሩና በጅቡቲ ምክንያት ነው። በወዳጅነታችን ምክንያት ጃንሆይ በ1924 (እ.ኤ.አ.) ብዙ መኳንንቶች ይዘው አውሮፓን የጉበኙ ጊዜያት ሄድኳርተራቸውን ፓሪስ ነበር ያደረጉት። ተፓሪስ ሉንዶን፣ ተፓሪስ ሮም እንደዚሁም ስዊድንን እየጉበኙ ይመለሱ ነበር።

የሂትለርና የጀርመን መነሳት ፈረንሳይን ስለአሰጋ፣ የፈረንሳይ ጠቅላይ ሚኒስትር መሲዬ ላቫል (Mr. Laval) ተጣልያን ጋር መቀራረብና ይልቁንም ሙሶሉኒን ተሂትለር ለመለየት፣ በብዙ መንገድ ሙሶሉኒን ለማስደሰት ፈለገ። በዚሁ አኳኋን ስለኢትዮጵያ ላቫልና ሙሶሉኒ አንድ ስምምነት ፈረሙ። ፍሬ ነገሩም ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ የሚያደርገውን ሁሉ ፈረንሳይ እንዳይቃወም ነው።

ጣልያን ኢትዮጵያን መውጋት ሲጀምርና ተዚያም በፊት ኢትዮጵያ ለሊግ ኦፍ ኔሽን የምታቀርበውን አቤቱታ ሁሉ እንዳይታይ፣ ፈረንሳይ ለጣልያን በመርዳት ሳቦታጅ ታደርግ ነበር።

በዚህ ጊዜያት የፈረንሳይ አገር የፓርላማ ኢሌክሽን ስለደረሰ የሦስት ዋና ዋና ፓርቲዎች፣ ራዲካል ሶሲያሊስት፣ ሶሲያሊስትና ኮሚኒስት (Radical Socialist, Party Socialist, Party Communist) የሚባሉት፣ ታላላቆቻቸው መሲዬ ሔሪዩ፣ ብሉምና ትራዘ የሚባሉቱ የላቫልን መንግሥት ፖለቲካ በመንቀፍ እሱን ለመገልበጥ ካምፔን ጀመሩ። በዚሁ ሁናቴ ላይ እንዳሉ በየስብሰባቸው እየተገኘሁ ላቫል ሙሶሉኒን ለማስደሰት ሲል ኢትዮጵያን በመሸጥ **የሴኩሪቲ ኮሌክቲቭን አላማ** /Secriate Collective/ ማድከሙን፣ የኢትዮጵያ አቤቱታ እንዳይታይ እያደረገ የሊግ ኦፍ ኔሽንን አላማና አቋሙንም እንዲዳከም፣ በዚህም

እኪ.ኒን እንደነሙሶሉኒና ሂትለር ያሉትን አግሬሰሮች እንዳበረታታና ያሰምም ጦርነት እንዲፋጠን ማድረጉን በዝርዝር ማስረዳቴ፣ ለፓርቲዎቹም የላቫልን መንግሥት ለመገልበጥ ደህና መሣሪያ መስጠት ለኢትዮጵያ ታላቅ ጥቅም እንደሚሰጥ ተረድቼ፣ ተፓርቲዎቹ አላፊዎች ጋር በየስብሰባቸው እየተገኘሁ ንግግር እንዳደርግ ሐሳብ አቀረብኩላቸው። እነሱም አመዛዝነው ሐሳቡ የሚረዳቸው መሆኑን ገብቷቸው፣ በስብሰባቸው የፈለኩትን ያህል እንዳስረዳ ፈቀዱልኝ። ተዚህ በኋላ በየስብሰባቸው እየተገኘሁ የኢትዮጵያን ሁኔታና የጣልያንን አግሬሽን፣ ይህም እንደዚሁ የታሰፈ ጊዜያት ማናቸውም አገር፣ ፈረንሳይም ጭምር፣ የኢትዮጵያ እድል እንዳይደርስባቸው በዝርዝር አስረዳ ነበር።

አንድ ቀን ሦስቱም ፓርቲዎች በየበኩላቸው ስብሰባና ልዩ ልዩ ዲስኩር ሲያደርጉ በየተራ እየሄድኩ በሦስቱም ሥፍራ ንግግር አድርጌ ነበር። ስብሰባውም ውስጥ የሚያስቀምጡኝ ተማሪዎች ጋር ነበር። ሲያስተዋውቁኝም፣ «ላቫል በኢትዮጵያ ላይ ያደረገውን ግፍ እንደዚሁም ኮሉክቲቭ ሴኩሪቲን እንዳጠፋ የኢትዮጵያ ሬፕሬዘንታቲቭ ያስረዳችኋል»፣ እያሉ ነበር። በማግስቱ በየጋዜጦቻቸው ላይ እንደፖስቲካቸው ዝንባሌ «እክሊሉ ሀብተወልድ፤ የኢትዮጵያ የኢንቴሌክቿአል ክፍል፣ የሠራተኞች ክፍል፣ የጦር ሠራዊት ክፍል ሬፕሬዘንታቲቭ፤ ይህን ተናገረ» እያሉ አተሙ። እነዚህም ጋዜጦች ፈረንሳይ አገር ይገኛሉ።

የኢሌክሽን ካምፔን በዚህ እኪ.ኒን ተደርጐ ተተዘጋ በኋላ የላቫል ፓርቲ ተረቶ ወደቀ። የሶሻሊስት ፓርቲ (Blum የሚመራው) አሸነፈ። የሶሻሊስት ፓርቲም ተሌሎች ፓርቲዎች ጋር ተስማምቶ ፍሮን ፓፑሌር /Front Populair/ የተባለውን ዩንየን አቋቁሞ፣ መንግሥት መሥርቶ ሥራውን ጀመረ። በዚህም ጊዜያት ኢትዮጵያ ተወራ ጃንሆይ ወደ ሎንዶን መጡ። ሲእን ብሉም፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩን፣ ሳነጋግረው «መቼም እኛ የመጣነው ውጊያው ታለቀ በኋላ በመሆኑ አዝናለሁ። ቢሆንም መቼም ቢሆን ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ ያላትን ይዞታ አናውቅም»፣ ብሉ አረጋገጠልኝ። በዚህ እኪ.ኒን በተሰጠውም ቃል ሌሎች መንግሥታት፣ እንግሊዝም ጭምር፣ የኢትዮጵያን መጥፋት ለጣልያን ሲያውቁላት፤. እምስቱን አመት ሙሉ ትልቁ ጦርነት እስቲነሳ፣ እኔ በፓሪስ የኢትዮጵያ ጉዳይ ፈጻሚ ሆኜ፣ ኢምባሲውም

ታወቀና [እንደማንኛውም ሉአላዊ ሀገር] ፓስፖርት እየሰጠ ማናቸውንም የኢምባሲ ሥራ ሲሰራ ቆየ። የኢትዮጵያ ስደተኞች ሁሉ ፓስፖርት ሲያስፈልጋቸው እኔ ዘንድ እየመጡ እሰጥ ነበር። የፈረንሳይ መንግሥትም ኦፊሴአል በሆነው ጥሪ ሁሉ፤ አምባሳደሮች በሚጠሩበት፤ የኢትዮጵያን ጉዳይ ፈጻሚ ይጠራ ነበር። ለምሳሌ፤ በ1938 እ.ኤ.አ. የእንግሊዝ ንጉሥና የእንግሊዝ ንግሥት በኦፊሻል ግብዣ ለጉብኝት ፓሪስ መጥተው ተሌሎች አምባሳደሮች ጋር እኔም ተጠርቼ ሄጄ ነበር። በፕሮቶኮሉ ደንብ የኢትዮጵያና የጣልያን ጉዳይ ፈጻሚ አቀማመጣቸው ጐን ለጐን ስለነበረ፤ እጠገቡ በምሆንበት ጊዜያት ጣልያኑ በጣም ሲቆጣ እኔም ኃይለ ቃል ስለተናገርኩት፤ ሁሉም ጭቅጭቁን ሰምተው፤ የፕሮቶኮሉ ሹም ሌላ የውጭ ጉዳይ ፈጻሚ /ኤጀንት/ በመካከላችን አስቀመጠ። ይህ ቀን ንጉሡን ለሰላምታ የምንጨብጥበት ጊዜ ነበር። በማታ እራት ግብዣም እንዲሁ ተደረገ። በሪሴፕሽኑ ጊዜያት ጣልያንን በመፍራት ሁሉም ሲሸሸኝ የፓርላማው ፕሬዝዳንት ሄሪዮ /President Hrriot/ (ብዙ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትር የነበሩት) ከሊኦን ብሉም ጋር ወደኔ መጥተው፤ እጄን ይዘው ወደ ቡፌው ወስደው፤ ስለ ኢትዮጵያ በረጅሙ አነጋገሩኝ። በማናቸውም [ኢትዮጵያን] እንደሚረዱም አረጋገጡልኝ። ይህንን በማግስቱ ለጃንሆይ ሉንዶን ራፖር አድርጌ ስለነበረ ፕሬዝዳንት ሄሪዮን የሥላሴን ኮርዶን ሸለሟቸው። ተዚህ በኋላ እኚህ ትልቅ ሰው ከፓርቲያቸው ጋር ኢትዮጵያን ሲረዱ ቆዩ። እንደዚሁም እነ ሊኦን ብሉምና ሌሉችም።

### 1.2.1 ተጋዜጠኞች ጋር ያደረኩት ግንኙነትና ኢትዮጵያን የሚረዱ እንዲቋቋሙ ያደረኳቸው ኮሚቴዎች

የውጊያው አንዱ መሣርያ ፕሮፓጋንዳ ስለሆነ ጣልያኖች በጋዜጣም፤ በሲኒማም፤ ገና ፕረሜቴፍ፤ ባርያ ሻጭ፤ አውሬዎች... እያሉ በራዲዮንም በኢትዮጵያ ላይ ልዩ ልዩ ፕሮፓጋንዳ ያደርጉ ነበር በዚህም እኳኋን እኛ የምንሄደው ኢትዮጵያን ለማሰልጠን ነው /Mission Civilization/ ይሉም ነበር። ፕሮፓጋንዳ ስላበዙ ሕዝቡ ስሜቱን ለኛ፤ ስሞታውን ወደነሱ አዙሮ ነበር።

ተልዩ ልዩ ጋዜጦች ጋር ግንኙነት እያደረግሁ እውነቱን እስረዳ ነበር። ኢትዮጵያ ተብዙ ዘመን ጀምሮ የክርስቲያን አገር መሆኗን፤

በስልጣኔውም ምክንያት እስታሁን ነጻነቷን ይዛ መቆየቷን፤ ባርያም እንደሌለ በሌላም ማስረጃ አስመሰከርኩ። ብዙ ወዳጆች ስለነበሩኝ አንዳንድ ጋዜጦች ይልቁንም የሦስቱ ፓርቲ ጋዜጦች ይህንን አወጡት።

ተወዳጆቼ ጋር (ሙሴ ጃንጉል፤ በኋላ እዚህ መጥቶ በማስታወቂያ ሚኒስቴር የፈረንሳይኛ ጋዜጣ አቋቁሞ ይሠራ የነበረው) እንደዚሁም ሌሎች ፈረንሳዮች ጋር ኢትዮጵያን የሚረዱ ሁለት ኮሚቴዎች እንዲቋቋሙ አደረግሁ። እነሱም በየጊዜው በብዙ ሺ የሚቆጠር ሕዝብ እየሰበሰቡ፤ ኢትዮጵያን የሚረዳ ንግግር እያደረግን የጣልያንን ግፍ እናስረዳ ነበር።

በተለይም ጦርነቱ ተተጀመረ ወዲህ አንዳንድ አገሮች ወደ ኢትዮጵያ የቀይ መስቀል ስለላኩ፤ [እነዚህ ወዳጆቼ] የፈረንሳይ መንግሥትም የፈረንሳይ የቀይ መስቀል ዶሊጌሽን እንዲልክ ቢጠይቁ መንግሥቱ ባለመፍቀዱ፤ ህዝቡ ገንዘብ እንዲያዋጣ አድርገው አንድ የቀይ መስቀል ርዳታ ዓይነት አልጋ፤ ልብስ፤ ሐኪም አርገው፤ የዶሊጌሽኑም አለቃ መሲዩ ጃንጉል ሆኖ ኢትዮጵያ መጥተው እርዳታቸውን አበርክተዋል። ይህም በኛ የቀይ መስቀል የታወቀና ምስጋና የቀረበበትም ነው። የኢትዮጵያ የቀይ መስቀል ጸሐፊም አቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ ነበር። ዶሊጌሽኑ ሚሽኑን ጨርሶ ሲመጣ ሙሴ ጃንጉል ራፖሩን እንዲያቀርብ ትልቅ ስብሰባ ተደረገ። በንግግሩም ጊዜያት፤ «ባርያ የሚባል በኢትዮጵያ አላየሁም፤ እንዲያውም የተረዳሁት የኢትዮጵያ ሕዝብ ተጣልያን ሕዝብ የበለጠ ነጻ መሆኑን ነው» አለ። በዚህም ጊዜ ታላቅ ጭብጨባ ተደረገ።

በነዚህ በሁለቱ ኮሚቴዎች ርዳታና መሥራችነት "ኒውስ ኦፍ ኢትዮጵያ" ወይም "ኑቬል ዲ ኢትዮጺ" የሚባል አንድ ጋዜጣ ተቋቋመ። በየጊዜው የኢትዮጵያን ፖዚሽንና የጣልያንን ግፍና አግሬሽን ያስረዳ ነበር። እኔም በየጊዜው ቢጋዜጣው እጽፍ ነበር። የዚህ ጋዜጣ አንድ በአርካይቭ አለኝ። የሁለቱ ኮሚቴዎች ስምም "Committee d' Action Ethiopiet, Assis Du People Ethiopie" ይባል ነበር።

## 2. በሊግ ኦፍ ኔሽን የኢትዮጵያ ዋና ጸሐፊ



አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በጄኔቭ የኢትዮጵያ ዴሊጌሽን ዋና ጸሐፊ ሆነው ሲሾሙ በ19ኛ ዓመት ዕድሜያቸው ላይ ነበሩ።

ይህንን የሚደረገውን ትግል በማየት ገና በልጅነቴና በትምህርት ላይ እንዳለሁ ጃንሆይ በጄኔቭ የኢትዮጵያ ዴሊጌሽን ዋና ጸሐፊ አደረጉኝ። የዴሊጌሽኑ መሪ ፊታውራሪ ተክለሃዋርያት ያን ጊዜ በፓሪስ ሚኒስትር የነበሩ ናቸው። ስለሙግትም ጄኔቭ የምንሄደው እሳቸውና እኔ ብቻ ነበርን። አማካሪ ሆነው የሚረዱን የታወቁት ፕሮፌሰር ገርዘ የኔ አስተማሪ ነበሩ። ይህንንም የሚያስረዳ መጋቢት 13/1935 እ.ኤ.አ. የተጻፈ የሱዊስ የደብዳቤ ወረቀት በአርካይቭ ይገኛል። በዚህ አኳኋን ተፊታውራሪ ተክለሃዋርያት ጋር ጄኔቭ እየሄድን ተጣልያን ጋር እንሟገት ነበር።

ፌታውራሪ ተክለሃዋርያት ተመልሰው ብላቴን ጌታ ወልደማርያም በሳቸው ፈንታ እንደተተኩ፣ በኋላ በኢትዮጵያ ኢምባሲ የፕሬስ አታሼ ሆኜ እንድሠራ ጃንሆይ ታዲሱ ውጊያ [ማይጨው] ላይ ባሉ ጊዜያት አንድ ቴሌግራም ለብላታ ወልደማርያም ላኩላቸው። እሳቸውም እምቢ ብለው [ወደ ኤምባሲው] አላስገባም አሉኝ። ቢሆንም እውጭ ሆቴል ተቀምጬ እንደ ፕሬስ አታሼ ሆኜ ስሰራ ነበር፣ ጋዜጠኞችን እየተገናኘሁ በማስረዳት፣ ኢንተርቪው በመስጠት። ለምሳሌ የላቫል-ሆየር ፓክት /Laval–Hoare Pact/ ን ሴራዎች በማጋለጥና በመሳሰሉት ስሰራ ነበር። ላቫል፣ የፈረንሳይ ጠቅላይ ሚኒስትር ላቫልና የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ውለተር ሆየር ስምምነት አድርገው፣ ኢትዮጵያ የሚበልጠውን አገር (ሐረርን፣ ሲዳሞን፣ ባሌን) ለጣልያን ሰጥታ ሌላውን ያማራ የሚባለውን (ጎንደር፣ ጎጃም፣ ትግራይ ...) አስቀርታ ተጣልያን ጋር እንድትታረቅ፣ አለዚያ ሌላ መውጫም እንደሌለና [ይህንን ካልተቀበለች] ሁለቱም መንግሥቶች ምንም እርዳታ እንደማያደርጉ፣ ይህንን ፕሮፖዛል በሚስጥር አዲስ አበባ በሚገኙት አምባሳደሮቻቸው አማካይነት ለጃንሆይ እንደ የመጨረሻ ውሳኔያቸው አድርገው አቀረቡ።

ይህን አደራረግ ተግርማዊነታቸው በመልክት ስንሰማ ማዳም ታቡደስ ለምትባለው የፓርቲ ራዲካል ጋዜጣ ዳሬክተር የነበረች የታወቀች ጋዜጠኛ በሚስጥር ገለጥኩላት። እሷም ወሬውን ይዛ ያበለጠ ነፃነት ወዳለበት ሉንዶን ሄዳ በጋዜጣና በራድዮ ገለጠችው። ጋዜጣው ሁሉ (Prime l'Agression) ለአግሬሽን ሽልማት ብሎ የላቫልንና የሆየርን ስምምነት እንደትልቅ ስካንዳልና ለሶሴቴ ዲናሲዎን እና ኮለክቲቭ ሴኩሪቲን አላማን ሁሉ የሚጥል መሆኑን በረጅሙ አስረዱ። በዚሁ ጉዳይ በእንግሊዝ ፓርላማ ታላቅ ክርክር ተደርጐ ሆየርም ተጠየቀ። እሱም እያሰቀሰ፣ «እኔ በእውነቱ ይህንን ያደረኩት ተኢትዮጵያ ለማዳን የሚቻለውን ለማዳን በማሰብ ነው። አንድም መንግሥት ሄዶ ለኢትዮጵያ የሚዋጋ ስለሌለ ነው፣ በሐቀኝነት ነው የሠራሁት፣ ይቅርታ እጠይቃለሁ» አለ። በዚህ አኳኋን የዓለም መሪዎች ሃሳቡን ስለተቃወሙና ጃንሆይም የእምቢታ መልስ ስለሰጡ ሃሳቡ ፈረሰ።

ይህንን ሁሉ በማደርግበት ጊዜያት ለምግብም ለሥራዬም ትረዳኝ የነበረችው ያኔ ወዳጅ የነበረችው አሁን ሚስቴ የሆነችው ማድሟዜል ኮሌቴ ሻላድ ነበረች። እሷም ያን ጊዜ ትምህርቷን ጨርሳ አስተማሪ ነበረች። በምታገኘው ደመወዝና ተአባቷም በምታገኘው እርዳታ የተቻላትን ያህል ድጋፍ ታደርግልኝ ነበር።

## 2.1 ተማይጫው ውጊያ በኋላ ጃንሆይ ወደጐሬ ሄደው ውጊያውን ይቀጥላሉ የሚል ወሬ በጋዜጣ ስለመጻፉና እኔም ወደጃንሆይ ጐሬ ለመሄድ መሰናዳቴ

ይህ ወሬ በሰፊው በጋዜጣ ስለተነዛ፣ በጀኔቭ ማኅበርም በሙግት ምንም ማግኘት ስላልቻልን፣ ያለው መንገድ ውጊያውን በብዙ ዓይነት በጥብብ መቀጠል መሆኑን ስለተሰማኝ ጃንሆይ ወደሚገኙበት ጐሬ ለመሄድ ቆረጥኩ። መንገዱም በሮያል ኤርላይን እስከሱዳን ሄዶ፣ ከዚያም በአባይ በኩል በመርከብ እስኪጋምቤላ መንዝ እንደሚቻል አጠናን። አሁን በማድሟዜል ሻላድ የገንዘብ ርዳታና በባልንጀሮቼ እነመሲዬ ሉካስ፣ ደኒአ፣ ሉጋር፣ ኒፍና በሌሎችም እገዛና እርዳታ የአውሮፕላን ቲኬት ገዛሁ። መሲዬ ሉካስም ከኔ ጋር ለመሔድ ቆረጠ። ማንኛውንም ኢኩዩፕመንት ድንኳን፣ መድሐኒት የመሳሰሉት ገዝተን ልንነሳ ሁለት ቀን ሲቀረን ጃንሆይ ወደ ሎንዶን ለመሄድ ጅቡቲ ደረሱ የሚል ወሬ በጋዜጣ ወጣ። በዚህም እኳኋን ምክንያቱን ስላላወቅነው ተስፋችን ተቆርጦ በሐዘን ላይ ወደቅን።

## 2.2 ጃንሆይ እየሩሳሌም እንደደረሱ በቴሌፎን ግንኙነት ማድረግና መሲዬ ማርሲል ግሬኦልን መሳክ

መሲዬ ግሬኦል (Griaule) የተባለ የፈረንሳይ ትልቅ ጸሐፊና ደራሲ ነበር። ብዙ መጽሐፍ ከመጻፉም ባሻገር ወደ ኢትዮጵያ በፊት መጥቶ ልዩ ልዩ አገር ጎንደርንም ጭምር ጐብኝቶ ሔዶ ነበር። ሲመለስም ሰው ኢቃጣዮች /Flambeours d'Home/ የሚባል መጽሐፍ ጽፎ ነበር። በመጽሐፉ ውስጥም «በድሮ ጊዜ በኢትዮጵያ አንዱ ቅጣት ሰም በተነከረ

ልብስ ሰውየውን [እጥፉ የተባለውን] አልብሶ ማቃጠል ነው» በማለት ጽፏል። ጣልያኖች የእኛን አውሬነት ለማሳየት ተሌሎች ዶኪሞና (መረጃዎች) መጽሐፎች ጋር ይህንን መጽሐፍ ለጀኔቭ ጉባኤ ለምስክርነት አቅርበው ነበር። በዚህ ጊዜ እሱም ተቆጥቶ፤ «እኔ ይህንን የጻፍኩት የልብ ወለድ ሮማንስቲው እንጂ እውነተኛ ሆኖ ለምስክርነት መቅረብ የለበትም» ብሎ፤ ለጀኔቭ ጉባኤ ፕሮቴስቴሽን አቅርቦ ነበር። ተዚያም በኋላ በየጊዜው እየተገናኘን በጋዜጣ ለኢትዮጵያ ካምፔን ያደርግ ነበር። ስለዚህ ይህ የታወቀ ደራሲ ጃንሆይ ዘንድ ሄዶ የውጊያውን አኳኋንና የጣልያኖችን ግፍ ተጃንሆይ ሰምቶ ለዓለም ቢያሰማ ጠቃሚ መሆኑን በመረዳት፤ ጃንሆይ እየሩሳሌም እንደደረሱ እሱ መጥቶ ሁሉንም እንዲነግሩትና እንዲጽፍ ሐሳቡን አቀረብኩላቸው። ጃንሆይም ሃሳቡን ተቀብለው ቶሎ ላክው አሉኝ። ገንዘብ አዋጥተን በፍጥነት በአውሮፕላን እንዲሔድ አደረግን። እሱም ተጃንሆይ ጋር በመርከባቸው /የእንግሊዝ የጦር መርከብ ነበር/ ተሳፍሮ እስከጅብላርተር ተጉዞ የሚነግሩትን ሁሉ በዝርዝር ጻፈ። ሲመለስም በሰማው ነገር በጣም ኢምፕረስ ሆኖ ነበር።

ተትንሽ ቀን በኋላም *"ተግርማዊነታቸው አፍ የተቀዳ"* የሚል መጽሔት አወጣ። /በፈረንሳይኛ ታይትሉ *"Ne weilleiees de la bouche máme de S.M.L. Empereur Haile Sellassie"* ነው።

በዚህም መጽሔት ውስጥ ጣልያኖች ያደረጉትን ግፍና ሃጢአት፤ በቦምብ ድብደባ ያቃጠሉትን ቤተክርስቲያን፤ ባዶ እግራቸውን የሚዋጉትን ወታደሮች እንደምን አድርገው በሂፐርት እንደፈጁ፤ ኢትዮጵያ ምንም አውሮፕላን፤ መድፍ ወይም ሌላ ሞደርን የሆን መሳሪያ ሳይኖራት «ለማሰልጠን ነው የምንሄደው» ያሉት ጣልያኖች እንደምን የአሕዛብ ሥራ በዚህ በክርስቲያን ሕዝብ ላይ እንዳደረጉ በማለት በዝርዝር አተተ። መጽሔቱም ፐብሊክ ኦፒኒየኑን በጣም ኢምፕሬስ አደረገ። እያነበቡም የሚያለቅሱ ነበሩ። ይህ መጽሔት ከተበተነ በኋላ የአውሮፓ ሕዝብ በበለጠ ለኢትዮጵያና ጃንሆይም ወደፊት ለሚያደርጉት አቤቱታ በጀኔቭ በሲምፖዚየም ድጋፉን ሰጠ። አምስቱን አመት ሙሉ ምንም እንኳ ጣልያን ልዩ ልዩ ፕሮፓጋንዳ

በኢትዮጵያ ላይ ቢያደርግ የሚሰማው አላገኘም። አውሬው ጣልያን፣ የሰለጠነው ደግሞ የኢትዮጵያ ሕዝብ ሆኖ ተገኘ። ይህ መጽሔት አውሮፓ ይገኛል። እጃንሆይ ቢብሎቴክም ሳይገኝ አይቀርም።

## 2.3 የጃንሆይ ሎንዶን መድረስና የኔ ለፓሪስ ሌጋሽን /ኢምባሲ/ ዋና ጸሐፊነት በጃንሆይ መወሰኑ ሚያዝያ 1936 እ.ኤ.አ.

ጃንሆይ ሎንዶን እንደደረሱ ወዲያውኑ ሄጀ ተገናኘሁና ለማናቸውም በሳቸው ዲስፖዛል መሆኔንና ለትግሉ ባለኝ አቅም ሁሉ ለመድከም ቁርጥ ሐሳቤ መሆኑን ገለጥኩላቸው። በአውሮፓ ያለውን ሁናቴ፣ ስለኢትዮጵያ ያለውን መንፈስ፣ ያደረግነውን ሁሉ በዝርዝር ከአስረዳሁ በኋላ፣ ወደፊት በምን አኳኋን ትግላችንን መቀጠል እንዳለብን፣ ስለአቅዳችንና ስለስትራቴጃችን በአገኘሁት ኤክስፒሪያንስና በአነጋገርኳቸው ታላላቅ ሰዎች /እንደነ ፕሬዝዳንት ሄርዮ ፓርዥገ፣ መሲዩ ግሬአል .../ ምክር መሠረት ሐሳቤን በሰፊው አስረዳሁ። በዚህም ጊዜ እነ አቶ ወልደጊዮርጊስ፣ ዶክተር ሎሬንሶ፣ መሲዩ እስፒንስር የአሜሪካን አማካሪ ነበሩ።

ተዚህ በኋላ በፓሪስ ሌጋሽን በዋና ጸሐፊ አቶ ዓለሙ ቸኮል ስፍራ እኔ ዋና ጸሐፊ ሆኜ እንድሠራና፣ ሥራውን በአስረዳሁት መሠረት እንድቀጥል አዘዙኝ። የማዘዣውንም ደብዳቤ አቶ ኤፍሬም /አሁን ብላታ/ ይዞ ፓሪስ ከኔ ጋር እንዲሄድ የጃንሆይንም ትእዛዝ ለብላቴን ጌታ ወልደማርያም በቃል ጭምር እንዲያስረዳ ታዘዘ። /ይህም የሆነበት ተዚህ ቀደም የፕሬስ አታሼ ብለው ጃንሆይ ያዘዙትን ወልደማርያም ስላልተቀበሉ ነው።/



ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ በሥራ ገበታ ላይ።

የዋና ጸሐፊውን ሥራ ተእቶ ዓለሙ እንደተረከብኩ /አሁ እየሩሳሌም ተዛወረ/ ሥራዬን ሥጀምር ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ታምሜአለሁ ብለው እቤታቸው ተቀመጡ፤ ቢሮም መግባት ተዉ። በዚህ አኳኋን ጃንሆይ ወደፓሪስ ሲመጡና ወደ ጀኔቭ ሲሄዱ የምቀበለው፣ አስፈላጊውንም ለጥበቃው ሁሉ ተፈረንሳይ መንግሥት ጋር እየተነጋገርኩ የማደርገው እኔው ብቻ ነበርኩ /ጃንሆይ መጽሐፍ ላይ ጃንሆይ ፓሪስ ሳሉ የተነሳው ፎቶግራፍ ይታያል/።

## 2.4 የብላቴን ጌታ ወልደማርያም ከድቶ ለጣልያን መግባትና የኔ ጉዳይ ፈጻሚ መሆን (1936 እ.ኤ.አ.)

ላይ እንደተባለው ሚኒስትሩ ህመም ምክንያት እያደረጉ ሥራ ስለማይገቡ እኔ እንደጉዳይ ፈጻሚ ሆኜ ሁሉንም ሥራ አስኪድ ነበር። ተፈረንሳይ ጋር ያለው ግንኙነት ፕሬስ፣ ፓስፖርት መስጠት፣ ... ነው።

በዚህ እንጊኔን ሦስት ወር ተቆየን በኋላ አንድ ቀን ማታ በ12 ሰዓት ቢሮ ሆኜ የፈረንሳይ የወሬ ወኪል ሃቫስ ደውሉ፣ ወሬውን ታውቃለህ ወይ ብሎ ጠየቀኝ። የማላውቅ መሆኔን ሲረዳ፣ በዚሁ እለት ሚኒስትራችን ጣልያን ኢምባሲ ሄደው ከሚስዮን ማድረጋቸውን (ጥገኝነት እንደጠየቁ) ገለጠልኝ። ነገሩን አላምን ብዬ ወዲያው እቤታቸው ሄድኩና ሚስታቸውንና ልጆቹን አግኝቼ ሚኒስትሩ የት እንደሄዱ ጠየኳቸው። እነሱም አናውቅም አሉ። /እነሱም እያወቁ ነበር፣ ምክንያቱም ስገባ ልጆቹ የፋሽስት ሰላምታ ሰጥተውኝ ነበር።/ እጠብቃለሁ ብዬ ተቀመጥኩ። ጋዜጣ እያነበብኩ ሁለት ሰዓት ሲሆን እሳቸው መጡ። እቤታቸው ሄጄ አላውቅም ነበርና ተገርመው ደግሞ ጋዜጣውን በማየት ተደናግጠው፣ «ወጣ እንዴ?!» አሉኝ። «ምኑ?» አልኳቸው፣ ዝም ሲሉ «ይደበቅ መስሉዎታልን? አዎን ወጥቷል፣ የእርስዎ መክዳት» አልኳቸው። «አሁን ያደረጉትን ሁሉ ምንም ሳይደብቁ ይንገሩኝ» አልኳቸው። «ምን ላድርግ? ልጆች አሉኝ፣ አዲስ አበባ ብዙ ቤት አለኝ። አንተ የተማርክ ስለሆንክ ሰርተህ ለመኖር ትችላህ፣ ምን ልሁን?» አሉኝ። እኔም፣ «ጣልያን ኢትዮጵያን ለመያዝ የመጣው የርስዎንና የሌላውንም ርስት ሊያከብር መስሉዎታልን? ደሞስ ምን ጐደሎት? ብዙ ገንዘብ ይዘው መጥተዋል። ኢትዮጵያንስ ለምን ያዋርዳሉ? አሁንም ሐሳብዎን ይለውጡ" ብዬ ተከራከርኳቸው። እሳቸውም፣ «ምንም ቢሆን አላደርገውም፣ ሦስት ሚሊዮን ሊሬ /3 Million Lire/ እስጥሃለሁ ብለውኛል» አሉ። ተዚህ በኋላ ቢሮ ሄደን ተጃንሆይ በስልክ ይነጋገሩ ብላቸው ሙሶሎኒ ይሰማኛልና እምቢ አሉ። እኔም በቁጣ፣ «ለጣልያን ገብተው ተመልሰው እኛ ኢምባሲ ነው ያሉት፣ እኛ መሬት ላይ እንዳሉ ነው፤ የፈለግነውን ልናደርግዎት እንችላለን። ይልቅስ ይምጡ!» አልኳቸው። ሚስታቸው እያለቀሱ፣ «ይህ ልጅ የተማረ ነውና የሚለውን ይስሙት፣ ቢሄዱ ይሻለዋል» ብለዋቸው፣ ወደ ቢሮ ሄድን።

በዚህ ጊዜ ጃንሆይ ጀኔቭ ነበሩ። ኢትዮጵያ አለች? የለችም? ተብሎ ታላቅ ክርክር ተደርጐ ለጊዜው አለች ተብሎ ለኛ ተፈርዶልን ነበር። ጃንሆይን በስልክ አግኝቼ ጉዳዩን ተገለጥኩላቸው በኋላ እሳቸውን እንዲቀርባቸው አዘዙኝ። ተቀረበም በኋላ ጃንሆይ፣ «አሁን ያቀረብንህ

ደስታችንን ልንገልጥልህ ነው። ኢትዮጵያ እለች ተብሎ ተፈረደልን» አሏቸው። እሳቸውም ዝም ሲሉ ጃንሆይ፣ «እዚያስ ምን ወሬ አለ?» አሏቸው። «እኔ ለጣልያን ገባሁ» አሏቸው። «ምነው?! ምን ጉደለህና ነው? እባ ለመግባት ተቆረጥህ ታሪካችንን ሳታበላሽ ሥራህን ተተውህ በኋላ አታደርገውም ነበርን?» አሏቸው። «አይ እኔ እርጌዋለሁ፣ በዚህም ቆርጫለሁ» አሉ። «ያደረግንልህን ሁሉ እረሳኸውን?» አሏቸው፤ ስልኩን ትተው ሄዱ። እኔም ስልኩን አነሳሁት፤ ሦስት ቀን ጃንሆይ ቢታገሱ ለመመለስ ልሞክር ብዬ ሃሳብ አቀረብኩላቸው። «ሃሳቡ ደህና ነው ግን የሚመለስ አይመስለኝም» ብለውኝ ተለያየን።

ተቢሮ ወደ ውጭ ብቅ ስል ጋዜጠኞች ተሰብስበው ጥያቄ አደረጉልኝ። ጥያቄውም፣ «ጃንሆይ ጀኔቭ ሸክትሪ ሲያገኙ ጣልያን ደግሞ እዚህ ሌላ ድል አገኘ። ይሄውም ሚኒስትሩ፣ ዋና ጸሐፊውም፣ በሙሉ ሌሎቹ የኢምባሲው ባልደረባዎች ለጣልያን ስለገቡ ነው» የሚል ነበር። ማነው እኔና ሌሎች ሠራተኞች መግባታችንን የነገራችሁ ብላቸው፣ «እሳቸው ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ለጣልያን ያስታወቁት በራሳቸው፣ በዋናው ጸሐፊና በሌሎች ሠራተኞች ስም ነው» ብለው፣ አረጋገጡልኝ። እኔም በፍጹም ውሸት መሆኑን ሳረጋግጥላቸው የደስታ ስሜት ይታይባቸው ነበር። ይህ መሆኑን ታወቅሁ በኋላ እነሱ ቃሌን እንዲቀዱና በራዲዮን ማታውኑ እንዲያስታውቁ፣ በማግስቱም በጋዜጣ እንዲያወጡት አንድ መግለጫ ሰጠኋቸው። ይሄውም ባጭሩ፣ «የኢትዮጵያ ሚኒስትር ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ዛሬ እጣልያን ኤምባሲ ሄደው በክዳት ገብተዋል እየተባለ ይወራል። ይህ ወሬ እውነት እንደሆን፣ ስህተት እንዳይኖር ቀጥሎ ያለውን ለማስታወቅ እወዳለሁ። የኢትዮጵያ ሌጋሽን ዋና ጸሐፊ የሆንኩት እኔ አክሊሉ ሀብተወልድ፣ ሌሎቹም ሠራተኞች በሙሉ ለኢትዮጵያና ለጃንሆይ ታማኝ ሆነን ተጣልያን ጋር ያለንን ትግል እንቀጥላለን። ሚኒስትሩም ገብተው እንደሁ በራሳቸው ስም ብቻ እንጂ በሊጋሽኑ ስም አይደለም። ተዚህ በቀርም እሳቸው የሚንታል በሽታ ታመው ሥራ ትተዉ፣ ቢሮም ታልገቡ ብዙ ወራቸው ነው፤ አውቀው ያደረጉት አይመስለኝም» የሚል ነበር። ይህ ዲክሌሬሽን ወዲያው በመላው ዓለም በራድዮን ተሰማ።

በማግስቱም ጋዜጦች የብላቴን ጌታ ወልደማርያምን ለጣልያን መግባት ሲገልጡ፣ ቀጥሎም የኔን መግለጫ በሚገባ አወጡት።

በዚህም አኳኋን እሳቸው የሜንታል በሽታ ታመው ለብዙ ወራት ሥራ አለመግባታቸውን ስገልጽ፣ በሌላ በኩል ዋናው ጸሐፊውና ሌሎችም ሠራተኞች ለጣልያን አለመግባታቸው ሲታወቅ፣ የወልደማርያም ለጣልያን ከድቶ መግባት ጣልያኖች የጠበቁትን ኢፌክት ሳይሰጥ ቀረ። /እኔን፣ እራሴን ለጣልያን እንድገባ በብዙ መንገድ ፈትነውኝ ነበር። አንድ ጊዜም ወደእኛ ታልገባህ ወንድምህን አካለወርቅን እና እናትህን እንገላቸዋለን ቢሉኝ፣ እኔ ታገሬ ስወጣ በልጅነቴ ነው፣ አላስታውሳቸውም፤ ብትፈልጉ ግደሏቸው አልኳቸው።/ ለጋዜጣ የሰጠሁትን መግለጫ በአጋጣሚ አርካይቭ ውስጥ አግኝቸዋለሁ። ቢጋዜጣው የወጣውም በጊዜው የወጡት ጋዜጦች ኮሌክሽን ውስጥ ይገኛል።

## 2.5 ወልደማርያም ያደረጉትን እንዲክዱ ለማድረግ ያደረኩት ጥረት

ጃንሆይ በቴሌፎን ሳነጋግራቸው እኔ ጉዳይ ፈጻሚ ሆኜ እንድሠራ ለፈረንሳይ መንግሥት ማስተዋወቁ ዘግይቶ፤ ሁለትና ሦስት ቀን ተሰጥቶኝ አሳባቸውን ሳስለውጥ ብዬ ሃሳብ አቅርቤላቸው፤ እሳቸውም ሃሳቡን ተቀብለውት እንደነበረ ላይ ተገልጿል። በዚሁ መሠረት ተወልደማርያም ጋር ንግግር አደረግሁ። «ጣልያን ኢምባሲ ሄደው ሦስት ሚሊዮን ሊሬ እንስጥዎታለን ያሉትን ይጠይቁ፤ ሁለተኛ ቤትዎን አዲስ አበባ ያለውን እንዲመልስልዎት ለግራዚያኒ ወረቀት እንዲሰጥዎት ይጠይቁ» አልኳቸው። እሳቸውም እሽ ብለው ሄዱ። ሲመለሱ «የሚቀበለኝ አጥቼ ታስጠበቀኝ በኋላ 3ኛው ጸሐፊ ነው የተቀበለኝ» አሉ። እሱም «ገንዘብ የሚባል የለም፤ ርስዎ ጌታ ነዎት፤ ስለቤትዎም እዚያ ተሄዱ በኋላ ይታያል» አለኝ፣ ብለው ነገሩኝ። እኔም «ይኸውሎት ያልኩት ሁሉ እውነት ነው። አሁንም ለታሪክዎም፣ ለልጆችዎም ሲሉ 'እኔ ታምሜ ነው የከረምኩት፣ የሠራሁትንም

አላውቅም፤ ለኢትዮጵያ ታማኝ መሆኔን አሁንም አረጋግጣለሁ' ብለው ያስታውቁ። መታመምዎንም ተሀኪም ምስክር ወረቀት ለማግኘት ተነጋግሬአለሁ» አልኳቸው። ተብዙ ክርክር በኋላ ሃሳቡን ተቀበሉ። ሀኪሙን ተወዳጆቼ አገኘሁ፤ ሰርተፊኬቱም ተሰናዳ። ጃንሆይ ነግሬአቸው በሥራው ተደሰቱ።

ሁሉም ተተሰናዳ በኋላ የጃንሆይ ልዩ ጸሐፊ የነበሩት ተሱንዶን ወደ አዲስ አበባ ሲመለሱ በፓሪስ በኩል አለፉ። የወልደማርያም ወዳጅ ስለነበሩ፤ «ተንግዲህ ወዲህ ጃንሆይ የሚመለሱና ኢትዮጵያም የምትድን መስሎሀልን? አብደሐል?! የአክሊሉን ሃሳብ አትቀበል፤ እኔም መግባቱ ነው፤ አንተም ግባ» ብለው፤ ሃሳባቸውን አስለወጧቸው። ይህንንም ለጃንሆይ አስታወቅሁ። ይህንን እላይ የተዘረዘረውን ሁሉ ጃንሆይ ደህና አድርገው ያስታውሱታል።

## 2.6 የኔ ጉዳይ ፈጻሚ መሆንና በአምስቱ ዓመት ተጃንሆይ ጋር ያደረኩት ትግል

የወልደማርያም መክዳትና ሃሳቡን ላለመለወጥ መቁረጡን ጃንሆይ ካወቁ በኋላ እኔ ጉዳይ ፈጻሚ ሆኘ እንድሠራ መሾሜን፤ የወልደማርያምንም መሻር የሚያስታውቅኦፊሴል ደብዳቤ ለፈረንሳይ መንግሥት ላኩ። የፈረንሳይ መንግሥትም ደብዳቤውን ተተቀበለና እኔም እንደጉዳይ ፈጻሚ በኦፊሴል አክረዲት ተሆንኩ በኋላ ሥራዬን ጀመርኩ፤ የደብዳቤው ኮፒ አርሺቭ ይገኛል። በአምስቱ ዓመት ጊዜ ተጃንሆይ ጋር ተስልፌ ለኢትዮጵያ ስታገል የፈጸምኩት ሥራ ብዙ መልክ ያለው ነው።

### 2.6.1 በገንዘብ ችግር ምክንያት የፓሪስ ሌጋሲዮን /ኤምባሲ/ እንዳይዘጋ ያደረኩትና የሰጠውም ጥቅም

የሉንዶን ኤምባሲያችን እንደተዘጋና ሀኪም ወርቅነህም ወደ ህንድ እንደሔዱ፤ የፓሪሱም እንዲዘጋ ሐሳብ ቀርቦ ነበር። ይህን ሃሳብ በብርቱ ተቃውሜና ተከራክሬ ጃንሆይም ሃሳቤን ተቀበሉኝ። ይህንንም ያደረኩበት፦

ሀ/ የሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዓላማና እንደዚሁም የሶሲዩቴ ዲናስዩን መሠረት ስለተናጋ፣ ማንም ኃይለኛ መንግሥት ትንሹን ቢያጠቃ ምንም እንደማይደረግ በማወቁ፣ ሂትለር በዚሁ ሁናቴ በመጠቀም ሌሎች ጐረቤት የሆኑትን አገሮች እንደነቸኮዝሎቫኪያ፣ ኦስትሪያ ያሉትን በኃይል ለመያዝ ስለሚሞክርና በዚህም አኳኋን ጦርነት እንደሚነሳ በማመን፣

ለ/ እስከዛሬም ድረስ ሌጋሲዮናችንን ሳንዘጋ እንቅስቃሴያችንን ከቀጠልን እንደድሮ ለመኖር፣ ነጻነታችንን ለማግኘት ያለንን ቁርጥ ሃሳብ ማሳየት ይሆናል፣

ሐ/ ትልቁ ጦርነት ሲነሳ ጣልያን ተሂትለር ጋር መሰለፉ ስለማይቀር እኛም እነሱን ተሚወጉት ጋር ተሰልፈን ትግላችንን ቀጥለን አብረን የማሸነፍ እድል አግኝተን አገራችንን ነጻ ለማውጣት እንድንችል፣

መ/ ኢምባሲያችንን ዘግተን ዝም ብለን የተቀመጥን ጊዜያት የሚበልጡት ያለም መንግሥታት የጣልያንን ይዞታ ስላወቁ ተረስተን እንደምንቀር ስላወቅሁ ነበር።

በዚህም አኳኋን ኢምባሲው እንዲቆይ ሲፈቀድ በገንዘብ ችግር ምክንያት የኢምባሲውን ሥፍራ ሁለት ጊዜ መለወጥ ግድ ሆነብኝ፤ ተ"Rue Columbertare Alfred" ተዚያም "Rue Tourmeput"። የመጨረሻው ቦታ ሁለት ክፍል ብቻ ነበረው፤ አንድ ቢሮና አንድ መኝታ ቤት። ቢሆንም የኢትዮጵያ ባንዲራ ቢሮው ላይ ይውለበለብ ነበር።

በኦፊሴል ለኢትዮጵያኖች ፓስፖርት መስጠት የምችል እኔ ብቻ ነበርኩ። ምክንያቱም በህግ የታወቀው ኢምባሲ ፓሪስ ያለው ብቻ ስለሆነ። በዚህም አኳኋን ለብዙ ኢትዮጵያኖች ፓስፖርት እሰጥ ነበር።

ተየሩሳሌም ሆነ ወይም ተሱዳን፣ ተሌላም ቦታ የሚመጡት ኢትዮጵያኖች የምቀበልና በቪዛና በሌላም በኩል ከፈረንሳይ ባለስልጣኖች ጋር እየተነጋገርኩ አስፈላጊውን እርዳታ ለማድረግ ችዬ ነበር። ለምሳሌ፣ ግርማዊት እቴጌ ተየሩሳሌም ወደ ሎንዶን ሲሄዱ በፈረንሳይ መርከብ እስከ ማርሴይ /የፈረንሳይ ፖርት/ ሄደ የኦፊሴል አቀባበል

እንዳደርግላቸውና በደህና በባቡር ተጉዘው፣ ፓሪስ ደርሰው ተዚያም ሎንዶን እንዲደርሱ አድርጊያለሁ። /የተሳፈሩበት መርከብ ወደጣልያን አገር የሚሄድ ሆኖ ይህንንም ሳያውቁት፣ መርከቡ ወደ እልጂ እንዲመለስ አድርጌ በሌላ መርከብ ማርሴይ እንዲገቡ አድርጌአለሁ። አለዚያ ጣልያን እጅ ይገቡ ነበር።/ እነራስ ካሣ፣ ራስ ብሩ፣ ቢትወደድ መኩንን፣ እነጀነራል ከበደ ሲመጡ እየተቀበልኩ አስፈላጊውን አድርጌአለሁ። በተለይም የኢትዮጵያ ቄሶች መድኃኒዓለምን ይዘው ተየሩሳሌም ሲመጡ ተቀብዬ፣ ሆቴል አሳድሬ፣ በማግሥቱ ወደ ሎንዶን እንዲደርሱ አድርጌአለሁ።

ልዩ ልዩ ግብዣ እያደረግሁ ታላላቅ ሰዎችንና የጋዜጣ ክፍሎችን እየጠራሁ የኢትዮጵያን ኮዝ ኬዝ አስረዳ ነበር። በተለይም የጃንሆይ ወጥ ቤቶች ተየሩሳሌም ሲመጡ ተቀብዬ እንድልካቸው ስለታዘዝኩ፣ ፓሪስ ለሁለት ቀን ስለሚቆዩ በነሱ በመጠቀም ትልቅ ግብዣ አድርጌ /የኢትዮጵያ ምግብ/ ስላሳ የሚሆኑ የፖለቲካና የጋዜጣ ሰዎች ጋበዝሁ። በማግሥቱም «የአንድ አገር ስልጣኔ በምግቡ ረቂቅነት ይታወቃል» ብለው በጋዜጣ አተቱ /La civilization d'un pays se re'commait a le rafinement de la consine/። ለዚሁም ግብዣ እነ እቶ ወልደጊዮርጊስ፣ ሎሬንሶና እቶ መኩንን ሀብተወልድ ተሎንዶን መጥተው ነበር።

በልዩ ልዩ ጉዳይ ለጃንሆይ ሃሳቤንና አድቫይዜን /በህግ/ እያቀረብኩ እረዳ ነበር። ለምሳሌ፣ በአንዱ የጄኔቭ ስብሰባ ጃንሆይ መልክተኛ የላኩ ጊዜያት መልክተኞቹን በቬሪፊኬሽን ኦፍ ፓወር ፕሮስጀር እናስወጣቸዋለን ብለው ጣልያኖች እስይመው ነበር። ይህንን እንደሰማሁ ለጃንሆይ «ራስዎ ይሂዱ፣ መልክተኛ እንዳይልኩ። ራስዎ የሄዱ እንደሆን እርስዎ ሄድ ስቴት ስለሆኑ ቬሪፊኬሽን ኦፍ ፓወር አይደረግም።» አላቸውም ሀሳቡን ተቀበሉ። የስዊስ መንግሥት ይህንን ጠርጥሮ፣ በጣልያንም ተገፋፍቶ አምባሳደሩ እኔ ዘንድ መጥቶ «በሚመጣው የጄነቭ ስብሰባ ጃንሆይ የመጡ ጊዜያት ስዊስ እንዲገቡ እንፈቅድላቸውም። ምክንያቱም የስዊስ መንግሥት ኢትዮጵያ የጣልያን ኮሎኒ መሆኗን ስላወቀ ነው» አለኝ። በዚህ እኳኋን አንድ ኖት ሰጠኝ። እኔም «ጃንሆይ

ስዊስ አይደለም የሚሄዱት፣ ለሶሴቲ ዲናስዎን እንጂ። እናንተ የማታውቁት አገር አገራችሁ እንዳይገባ የፈለጋችሁ ጊዜ ማ በሩ ሌላ አገር እንዲዛወር አድርጉ» ብዬ መለስኩለት። በዚህም አኳኋን ጃንሆይ እንዲሄዱ መከራ እሳቸውም ቆርጠው ሄዱ። የስዊስ መንግሥትም ምንም ሳያደርግ ቀርቶ ጃንሆይም ጉባዔ ላይ ተቀምጠው ለኢትዮጵያ ክርክራቸውን አቀረቡ።

እንደዚሁም ጣልያኖች በኢትዮጵያ በማናቸውም ክፍለ ግዛት ያለውን በሙሉ አገሩን ይዘነዋል ብለው ስለተማጉቱ፣ ጉሬ ላይ እነደጃዝማች ወልደጻድቅ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆነው ገዥርናንስ መኖሩን የሚያስረዳ ልዩ ልዩ ዶኩሜንትና ተዚያም ለጋዜጦች ሁሉ የሚላክ /በፖስጣ/በመቶዎች የሚቆጠሩ ዶክመንት ይዘው ለነቢትወደድ ጌታቸው፣ ብላታ ኤፍሬም ደረጀ፣ የብላቴን ጌታ ህሩይ ልጅ ተፓሪስ እንዲላፉሩ አድርጌ ነበር። ካይሮ ሲደርሱ ቢትወደድ ጌታቸው ለጣልያን ገቡ፤ ዶክሜንቱና ወረቀቱ ግን በብላታ ኤፍሬም እጅ ስለነበረ ጣልያኖች ሳይዙት ቀሩ።

እላይ እንደጠቀስኩት የኮለክቲቭ ሴኩሪቲ ዓላማ ስለተደመሰሰ ሂትለር በራሱ ሃሳቡን ፈጸመ። መጀመሪያ ራናኒን (Rhineland)፣ ቀጥሎ ኦስትሪያን፣ ቀጥሎም ቼኮዝሎቫኪን ያዘ። በዚህ ጊዜያት ሁሉ ምንም እነኚህ አገሮች የፈረንሳይ አላይ ቢሆኑም ፈረንሳይም፣ እንግሊዝም አልተንቃነቁም። በመጨረሻም /1940 እ.ኤ.አ./ ሂትለር ዳንዚግንና ፖሎኝን (ፖላንድ) ያዘ። በዚህ ጊዜያት እንግሊዝና ፈረንሳይ በጀርመን ላይ ጦርነት አስታወቁ።

ጣልያን ወደ ጦርነቱ መግባቷን /ተጀርመን ጋር ተሰልፋ/ የማይቀር መሆኑን በመግለጽ በጊዜው ጠቅላይ ሚኒስትር ከነበረው መሲዩ ፖል ሬና ቀጠሮ ጠይቄ አግኝቼው፣ «ጣልያን ጦርነት መግባቷ ስለማይቀር፣ አሁኑኑ እሷ ስትገባ ሥራ ላይ የሚውል የአልያንስ ውል ኢትዮጵያ፣ ፈረንሳይና እንግሊዝ እንዋዋል» አልኩት። እሱም ሳቅ ብሎ፣ «ይህ ያንተ ምኞትና ሕልም ነው። ጣልያን ምንም ጊዜ ቢሆን ጦርነት አትገባም» አለኝ። እኔም «መግባቷ የማያጠራጥር ነው፤ የስጣችኋትን ሁሉ አልበቃኝም ብላ እምቢ ያለች ለምንድነው?» አልኩት። «ምን አለ፣

ጣልያን እንደ ምኞትህ የገባች እንደሁ መጥተህ እንገናኝና ያኔውኑ እናደርጋለን፤ ግን ጉዳዩን በሚስጥር ጠብቅ» አለኝ። እስተዚያም ድረስ ሌሎችን የውጭ አገር ሰዎች ሁሉ ወይ ታገር እንዲወጡ ወይም ለፈረንሳይ እንዲዋጉ ትእዛዝ ስለተሰጠ እዚህ አገር ያሉትን ኢትዮጵያኖች /ብላታ ኤፍሬም፤ ብላታ ዘውዴ፤ አቶ መኮንን፤ አቶ መለስ አርአያ ሥላሴ፤ ሥዩም ብርሃኔና ሌሎችም/ ለወደፊት ያገለግላሉና እንዳይነኩ ብዬ ትእዛዝ ይሰጥ ብዬ ጠየቅሁ። እሱም፤ «አንድም ኢትዮጵያዊ እንዳይነካ በሚስጢር ትእዛዝ እሰጣለሁ» ብሉ፤ አረጋገጠልኝ። ትእዛዙም በምስጢር ለኮሚሣሪያዎቹ ሁሉ ተሰጥቶ ኢትዮጵያኖች እስከ መጨረሻው አልተነኩም።

በያሉበት ያሉትን የኢትዮጵያ ስደተኞች የሚረዳ የኢትዮጵያ ስደተኞች የዓለም ማ በር የሚባል /Association International en Refuqis Ethiopias/ ተአቶ መኮንን ጋር አቋቁመን ነበር። ይህ ማ በር ገንዘብ እየሰበሰበ በብዙ ሺህ የሚቆጠር ፍራንክና ፓውንድ በያሉበት አከፋፍሏል። ይህም ማንም ሰው ያወቀው ታላቅ ርዳታ አድርጓል። /ፋይሉን ማየት ይቻላል።/

# 3. የጣልያን ጦር መግባት

የሂትለር ጦር ፓሪስን ለመያዝ ትንሽ ቀን ሲቀረውና ሂትለር በማሸነፍ ላይ ሳለ ጣልያን ተጀርመን ጋር ተሰልፋ ጦርነቱ ውስጥ ገባች። ፖል ሬናን ወዳያውኑ ቀጠሮ ጠይቁ ቀንና ሰዓት ቀረጠልኝ። በቀጠሮ ቀን ስሄድ ሴሲቱን የፈረንሳይ መንግሥት ፓሪስን ለቆ ወደ ቦርዶ መሄዱን ነገሩኝ። ይህም ፓሪስ ሊያዝ አንድ ቀን ሲቀረው ነበር።

ወዲያውኑ ስመለስ ሰቱም፣ ባንኩም፣ ጋራጁም፣ ሁሉም ተዘግቶ እንዳንዱ ወደ ቦርዶ ተዛውሯል የሚል አየሁ። ተቦምብ ለማዳን በባንክ ኡፍር ያስቀመጥኩትንም አንዳንድ የአርሽብ ወረቀት ለመፈለግ ብሄድ እሱም ተዘግቶ አገኘሁ። ፓሪስን ጀርመኖች እንዲሁም ጣልያኖች ሳይዙት ተሦስት ባልንጀሮቼ /መኩብብ፣ ሥዩምና ሉቃስ/ ጋር በቢስክሌት ተፓሪስ ወጥተን ወደ ቦርዶ ተጓዝን። ቢስክሌቱን ለመግዛት የቻልኩት በማድሚዜል ኮሌቴ እርዳታ ነው። አሥር ሚሊዮን የሚሆን ሕዝብ በመሸሽ መንገድ ላይ ስለሚገኝ ተነመኩብብ ጋር ተጠፋፍተን ቦርዶ አብረን ለመድረስ የቻልነው እኔና ሉቃስ ብቻ ነበርን። በመንገድም ብዙ ውጣውረድ ደርሶብን፣ እንዲያውም የፈረንሳይ ወታደሮች ሴሲት እኛ መብራት በማብራታችን እንድንገደል አዘው፣ ሳይገድሉን ጀርመኖች ስለደረሱ ዳንን።

ወደ ቦርዶም የሄድኩት እንግሊዞችን የሚያሳፍር አንድ መርከብ ስላለ በዚያ ተሳፍሬ ወደ ጃንሆይ ለመሄድ ነበር። ግን እኛ ጧት ስንደርስ መርከቡ ማታ ሄዶ ተገኘ። በመጨረሻው መርከብ አንድ የፈረንሳይ መንግሥት ዲፕሎማት ሚሄድ መሆኑን ስሰማ ወደ እንግሊዝ አገር እንድሔድ የይለፍ ወረቀትና ማንኛውንም እርዳታ እንዲያደርግ ብጠይቀው፣ «እኛ አሁን ተሸንፈናል፣ ምንም ማድረግ አንችልም። ደግሞ በአደረግነው የአርሚስትስ ውል መሠረት የጣልያንና የጀርመን ጠላት የሆነ አገር ዜጋ ፈረንሳይን ለቆ እንዳይሔድ ውል ገብተናል። ከዚህ መሔድ አትችልም» አለኝ። «ለጣልያን አሳልፋችሁ

ልትሰጡኝ ነውን?» ይህ ተዓለም ህግጋት ውጭ መሆኑን ገልጬ ፕሮቴስት አደረግሁ።

የፈረንሳይ አዲስ መንግሥት ከፒተ ወደ ቪሽ እንደሔደ እኔም በድንኳን ውስጥ ቆይቼ ወደዚያው ተከትዬ ሄድኩ። እዚያም ጠቅላይ ሚኒስትር የነበረው ላቫል ስለነበረ እንደገና ተፈረንሳይ ለመውጣት ጥያቄ አቀረብኩ። እሱ የነሢትለር ሰው ስለነበረ፤ እንዲያውም አሁን ፈረንሳይ ኢትዮጵያን ስለማታውቅ ፓስፖርትህ መወሰድ አለበት ብሎ ፓስፖርቴን ነጥቆ፤ ማርሴይ ሬዚዶንሴ ፊክሴ (ቋሚ ነዋሪ) አርጉ ተዚያ እንዳልንቃነቅ አዘዘ።

ቢሆንም እኔ ሌላ ፓስፖርት አዘጋጅቼ በድብቅ ቪሽ እየመጣሁ፤ ተውጭ አገር አምባሳደሮች ጋር ንግግር እያደረግሁ፤ ተፈረንሳይ አገር ለመውጣት አደክም ነበር። ዘዴው ኢትዮጵያ ሳይሆን ሌላ አገር ለመሰደድ ተብሎ ቪዛ አግኝቶ መውጣትና በኋላ ጃንሆይ ወዳሉበት ለመሄድ ነበር። በዚህ አኳኋን የአሜሪካንንና የሜክሲካን ቪዛ አግኝቼ ነበር። ግን በፓስፖርቴ ተፈረንሳይ መውጣት አልተቻለም።

ተብዙ ችግር በኋላ ማርሴይ ያለው የኮሎምቢያ ቆንሲል ሁናቴዬ አሳዝኖት የኮሎምቢያ ፓስፖርት ሰጠኝ። ይህም ዜግነቴ ኮሎምቢያዊ ሆኖ ስሜም ቶማስ ወልድ ተብሎ ነው። ይህ ፓስፖርት እንዲጋጣሚ እቤት ይገኛል።

በዚህ ፓስፖርት ተማርሴይ አገረ ገዢ ጋር በሚስጥር ተነጋግሬ በብዙ ውጣውረድ ፈረንሳይን ለቅቄ ለመውጣት ቻልኩ። መሄጃዬም በስፔንና በፖርቹጋል ነበር። ፖርቹጋል ያንጊዜ ኒውትራል የእንግሊዝም ወዳጅ ስለሆነ እዚያ ተደረስኩ በኋላ ማንኛውንም ርዳታ አገኘሁ። ከፈረንሳይ ከመነሳቴ በፊት ፖርቹጋል ስደርስ የራሴን ፓስፖርት እንዳገኝ ማርሴይ ለነበረው ለአሜሪካን አምባሳደር ያን ጊዜ ኢሚራል ሌይ የሚባል /በኋላም ስቴት ሸፍ እፍ እታች የሆነ/ ፓስፖርቴን ሊዝቦን ኤምባሲያቸው እንዲልክልኝ ሰጥቸው እሱም እሺ ብሎ ወስዶ ነበር። ሊዝቦን ስደርስ ወዲያውኑ ኤምባሲ ሄጄ ፓስፖርቴን አገኘሁ።

እንግሊዝ ኤምባሲ ሄጀ ወደ ኢትዮጵያ ለመሄድ እርዳታ እንዲያደርግልኝ፣ ተዚህም በቀር ፈረንሳይ አገር የቀሩትን ኢትዮጵያኖች /መክበብ፣ አቶ መኰንን/ ለማውጣት መሥራት ስላለብኝ እርዳታውን ሁሉ እንዲያደርግልኝ ጠየቅሁ። እሱም ያንጊዜ ጃንሆይ አዲስ አበባ ገብተው ስለነበረ ቴሌግራም አድርጕ ለመርዳት ፈቃደኛ መሆኑን ገለጠልኝ። መርከብ ስለማይገኝ በማንኛውም ፕራዮሪቲ ተሰጥቶኝ መሳፈር እንድችል ተእንግሊዝ አገር ተአቶ አማኑኤል ጋር /ያን ጊዜ የጃንሆይ ወኪል/ ተጻጽፌ ፕራዮሪቲ ወረቀት ሰጡኝ።

ፈረንሳይ ከቀሩት ኢትዮጵያኖች ጋር እየተጻጻፍኩ እነሱም ለመውጣት የሚችሉበትን ተየኢምባሲዎቹ ጋር ተነጋግሬ ለመውጣት እንዲችሉ ታደረግሁ በኋላ፣ መርከቡ እንደተገኘ ተሁለት ወር በኋላ በአፍሪካ ዞሬ ወደ ሞምባሳ ለመድረስ ቻልኩ። ተኔ ጋር ያለው መሲዬ ሉቃስ ብቻ ነበር። አዲስ አበባ የደረስኩት በ1941 /እ.ኤ.አ./ መጨረሻ ነው።

ተጃንሆይም ተተነጋገርኩና ሁሉንም የደረሰውን በሙሉ ራፖር ታደረኩላቸው በኋላ፣ በጽሕፈት ሚኒስቴር አንድ ቢሮ ሰጥተውኝ በህግ አማካሪነት ልዩ ልዩ ትእዛዝ እየሰጡኝ እሠራ ነበር። ይህም ቢሮ የተሰጠኝ ሁለትና ሦስት ወር ሥራ ፈትቼ ተቀምጬ ተዚያም በኋላ አንድ ራፖር ማሰናጃ መክፈት ስለሚገባንና ስለ አቋማችን ለጃንሆይ ራፖር ታደረግሁ በኋላ ነው።

## 3.1 ምክትል የጽሕፈት ሚኒስትር

የጽሕፈት ምክትል ሚኒስትር በነበርኩበት ጊዜያት ብዙም ሥራ ባይኖር አንዳንድ ጉዳይ ፈጽሜአለሁ።

ሀ/ የጃንሆይ የሕግ አማካሪ እንደመሆኔ፣ ለየመሪዎቹ የሚሄደውን መልክትና የሚደረገውን ዲስኩር ማዘጋጀት፣

ለ/ የመጀመሪያውን የሚኒስትሮች ሥልጣንና ተግባር፣ በነጋሪት ጋዜጣ የወጣውን፣ ተመስዬ ማቲው ጋር እኔ ነኝ የሠራሁት፣

ሐ/ የኢትዮጵያ ብሔራዊ ገንዘብ እንዲሁም ባንክ እንዲቋቋም ሲደረግ የእንግሊዞችን ሃሳብ በክርክር አሸንፌ ባንኩም እዚህ አገር ዋና ቢሮው እንዲሆን፣ የቦርድ አባሎችም ኢትዮጵያኖች እንዲሆኑ አድርጌአለሁ። ዝርዝሩ ብዙ ነው፤ ዶክመንቱ ሁሉ በአርካይቭ ይገኛል። ፍሬ ነገሩ ግን ያንጊዜ የምንሠራበት ገንዘብ ኢስት አፍሪካን ሽልንግ ነበር፤ የኢትዮጵያ ገንዘብ ገና አልወጣም። የ1944 /እ.ኤ.አ./ ውል እንግሊዞች በኛ ላይ የፕሮቴክሽን ነክ መብት ይሰጣቸው ነበር። /ያለነሱ ፈቃድ አማካሪ አለመቅጠር፣ የኢትዮጵያ ባንክ ሥፍራው እንግሊዝ አገር ሆኖ የቦርዱም አባሎች በእንግሊዝ ንጉሥና በጃንሆይ ስምምነት እንዲሾሙ፣ መሰብሰቢያውም ሎንደን እንዲሆን፣ በዚህ አኳኋን ወርቃችንን ሎንዶን አስቀምጠን እነሱ ወረቀት እያተሙ እንዲሰጡን። አንድ ቀን ብንጣላም ሁሉንም ሊክለክሉን ይችላሉ ማለት ነው።/ ያንጊዜ ኢትዮጵያ የነበሩት የእንግሊዝ አማካሪዎች በላንግፎርድ መሪነት፣ አንድ አሥራ ሁለት ይሆኑ ነበር። እሱና ሌሎች አማካሪዎች ሃሳባችንን ታልተቀበላችሁ ኢስት አፍሪካ ሽልንግም እንሰጥም ብለው መግባቢያም ጠፍቶ፤ ታላቅ ክራይሲስ ደርሶ ነበር። አማካሪዎችና እኛ ተሰብስበን ተነጋግረን ሃሳብ ለጃንሆይ እንድናቀርብ ሃሳብ አቀረብኩ። ሃሳቡን ተቀበሉት። በቢትወደድ መኰንን ሰብሳቢነት ተኔ ጋር ጸሐፊ ትእዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ደስታ ነበሩ። ተብዙ ክርክር በኋላ ባንኩም አዲስ አበባ እንዲሆን፣ የቦርዱም አባሎች በጃንሆይ እንዲሾሙ ተስማምተን የተባበረ ሃሳብ አቀረብን። በዚህ አኳኋን አሁን ያለን የኢትዮጵያ ዶላርና ብሔራዊ ባንክ ተቋቋመ። /ፕሮሲቨርባሉን ማየት ይጠቅማል።/

መ/ «ኢትዮጵያ አዲስ ኢትዮጵያ ናት፤ የድሮዋ ጠፍታ ስለነበረ የድሮው አዋጅ ሁሉ እንደገና መታወጅ አለበት» ብለው እንግሊዞች ጠይቀው ነበር። በዚህ ጊዜ በሚኒስትሮች ምክር ቤት «ኢትዮጵያ መቼም አልጠፋች፣ ጦርነቱን እንደቀጠልን ነበር። እስታሁንም አርሚስትስም፣ የሰላምም ውል ተጣልያን ጋር አልፈረምንም፤

ስለዚህ የዱሮው አዋጅ ሁሉ የረጋ ነው» በማለት ስለተከራከርኩና ሃሳብ ስላቀረብኩ ተእንግሊዞች ጋር እንድከራከር ታዘዝሁ። ተእንግሊዞች ጋርም ብዙ ክርክር ስናደርግ ቆይተን ማሸነፊያ ያገኘሁት በ1944 ውል ጃንሆይ ሲፈርሙ በሕገ-መንግሥቱ በተሰጠኝ ሥልጣን መሠረት /1930 እ.ኤ.አ. የወጣው የመጀመሪያው ሕገ-መንግሥት/ ስለሚል የዱሮው ሕግ ሁሉ ተረጋ ይህም ሕገ-መንግሥት አይረጋም ማለት ነው። በዚህም እኒኒን የ1944 ዓ.ም. ውል አይረጋም ስላቸው የዚህም ተከታይ ውጤት ስለገባቸው፣ እውነትህ ነው ብለው ሃሳቤን ተቀብለው ኢትዮጵያ አዲስ አለመሆኗን ስምምነታችንን ፈርመን ለጃንሆይ አቀረብን። በነሱ አስተያየት አዲስ ኢትዮጵያ የሆነች ጊዜ ጠረፉን፣ ሌላውን ሁሉ ለመለወጥ ነበር። /ፕሮሲቨርቫሉን ማየት።/

# 4. ምክትል የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በኋላ ሚኒስትር 1936—1942

የውጭ ጉዳይ ምክትል ሚኒስትር ሆኜ በምሠራበት ጊዜያት ሚኒስትር ስለሌለ በሕጉ መሠረት የሚኒስትሩን ሥልጣን ይዤ ስሠራ ነበር። በኋላም የሚኒስትሩ ታይትል ተሰጠኝ። ስለዚህ ምክትል የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርም ሆን ወይም ሚኒስትር ሁኔታውን አይለውጠውም።

ምክትል የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ወይም ሚኒስትር በነበርኩበት ጊዜያት የፈጸምኩትን ታላላቅ ጉዳዮች በአጭሩ ከዚህ ቀጥሎ ይዘረዘራል። /አንድ ነገር ማስታወስ የሚገባኝ ደግሞ የተማረና ዲግሪ ያለው — በውጭ ትምህርት — ኢትዮጵያኖች በጣም ትንሽ ነበሩ፤ ተአምስትና ተስድስት አይበልጡም ነበር። እውጭ ጉዳይ ስገባ አንድም ዲግሪ ያለው የለም ነበር። አሁን ያሉት ሚኒስትር የሆኑት /ተመሣክላቸው/ ኤርትራ ተተመለሰች በኋላ ነው እ.ኤ.አ. በ1952። ስለዚህ ተዓለም መንግሥታት ጋር ስሟገት ብቻዬን ነበርኩ። ብዙ ጊዜም ያለጸሐፊ እንኳን ብቻዬን ዓለምን ስዞር ነበር። ይህን ሁኔታ ያንጊዜ የነበሩት ሁሉ ያስታውሱታል።



በጠቅላይ ሚኒስትር ቢሮ፤ ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን፣ አቶ አክሊሉ፣ ጠሚ ቢትወደድ መኮንን እንዳልካቸው፣ ዶ/ር አምባ ወልደማርያም፣ አቶ አማኑኤል አብርሀም፣ አቶ ምናሴ ለማ፣ አቶ ጴጥሮስ ሳህሉ።

መጀመሪያ ሥራዬ ኢትዮጵያ ያለችበትን ሁናቴ ቅኝት ማድረግና ወደፊትም ማድረግ የሚገባትን ማጥናትና ፕሮግራም ማውጣት ነበር።

ሀ/ ጦርነት ላይ ነን፤ ምንም ጣልያን ተሸንፋ ተኢትዮጵያ ብትወጣ፤ የአርሚስትስም ሆነ የሰላም ውል ተጣልያን ጋር ስላልፈረምን በሕግ በኩል ጦርነት ላይ እንዳለን ነው። ተዚህ በቀር ሌሎቹ መንግሥቶች ተጀርመን፤ ጣልያንና ጃፓን ጋር ጦርነት ነበሩ።

ለ/ ኢትዮጵያን እንደ ጣልያን ግዛት ሆና ያውቋት አገሮች፤ ተተዋጊዎቹ ውስጥ እንደ እንግሊዝ ያለ፣ ኢትዮጵያን በተዋጊዎቹ ሰላዮች ተጠላት የተያዘች አገር ዓይነት ይቆጥሩዋት ነበር /Enemy Territory occupied by ally/። እ.ኤ.አ. በ1942 እንግሊዞች ያስፈረሙን ውል ይህንን ይመስላል። ኦጋዴንን ይዘዋል፤ ባቡሩን ይዘዋል፤ የኢትዮጵያን አርሚ በሞትም ይዘዋል። ያለእንግሊዝ አማካሪ የለንም፤ ሌላ ለመቅጠር የነሱ ፈቃድ ያስፈልጋል፤ እንድም አውሮፕላን ያለነሱ ፈቃድ ወደ ኢትዮጵያ አይገባም።

ሐ/ መጀመሪያ ይህንን ውል መስወጥ ተግባራችን ነበር። ይህንን የመጀመሪያ ሥራዬ እንዲሆን አቀድሁ፤ ኦጋዴንን፣ ባቡሩን ለመመለስ ጭምር።

መ/ ጦርነቱ ሲያልቅ፣ ለሰላም ጉባዔ አባል ለመሆንና ጥያቄያችንን ሁሉ ለማቅረብ ታሁኑ በብርቱ መሥራት፤

ሠ/ ወደፊት በጀኔቭ ማ በር ፋንታ ለሚቋቋመው አዲስ የዓለም ማ በር ተካፋይና መሥራች ለመሆን አሁኑኑ መሥራትና መሰናዳት፤

ረ/ አፋምቦን፤ ፈረንሣዮች የወሰዱብንን፤ ለመመለስ መሥራት፤

ሰ/ ጋምቤላን ለመመለስ መሥራት፤

ሸ/ ተጐረቤት አገሮች ጋር ያለንን ጠረፍ ዲሊሚት ለማድረግ መድከም። ምክንያቱም በሱማሊያና በኢትዮጵያ መካከል ዲሊሚቴሽን ስለሌለ ነው ወልወል የኛ ነው ብለው ጣልያኖች ጦርነት ያነሱት። የኢትዮጵያ ጠረፍ ተእንግሊዝ ሱማሌ በቀር ማናቸውም ዲሊሚት አልሆነም፤ ተኬንያ፣ ሱዳን፤ ጅቡቲ፣ የጣልያን ሱማሌ ጋር ዲሊሚቴሽን የለም። በዚህም ምክንያት

ኢንስዳና ግጭት ሊኖር ይችላል። /አንድ ሰው የቦታውን አጥር ደህና አድርጐ መሥራት እንዳለበት ሁሉ።/

ቀ/ በውስጥ በኩል የኢኮኖሚክና የሶሻል ሪድሬሲንግ ማድረግ አስፈላጊ እንደነበረ፤ በትምህርትም በኩል ብዙ መሥራት እንዳለብን፤ ሕገ መንግሥታችንንና ሌሎቹን ሕጐች በጣም ማሻሻል እንዳለብን። ይህንን ሁሉ ታላደረግን ኢትዮጵያ በዓለም ተገቢ ሥፍራዋን እንዳታገኝ ተረድቸው ነበር።

## 4.1 የጥር 31/1942 እ.ኤ.አ. ተእንግሊዞች ጋር የተደረገው የጦር ስምምነት በ ዳር 19/1944 ስምምነት እንዲተካ ያደረኩት አኳኋን

አላይ እንደተመለከተው ይህ ውል እንግሊዞች እንደተያዝን የሆን ዓይነት መልክ ይሰጣል። በውሉ መሠረት

- የእንግሊዝ ወታደሮች በየትም ሥፍራ ሊያዙ ይችላሉ፤
- በኢትዮጵያ ማንኛውም ሥፍራ ለመያዝ መብት ተሰጧቸዋል፤
- ማንኛውም አውሮፕላን ያለ እንግሊዞች ፈቃድ ኢትዮጵያ አይገባም፤
- አማካሪዎቹ ሁሉ እንግሊዞች ናቸው፤ ያለነሱ ፈቃድ ሌላ ማንንም መቅጠር አንችልም፤
- እንግሊዞች ወይም ሌላ የውጭ አገር ሰው የእንግሊዝ ዳኛ የሌለበት ሊፈረድበት አይቻልም፤
- የኦጋዴን ሪዘርቭድ ኤርያ በነሱ እንደተያዘ ነው፤
- ባቡሩም በነሱ እጅ ነው፤
- የእንግሊዝ አምባሳደር ሌሎች አምባሳደሮች ላይ ፕሬዮሪቲ አለው፤
- የእንግሊዝ የጦር አዛዥ በሌሎች ሚሊቴሮች ላይ ፕሬዮሪት አለው፤ እንደዚሁም ሌላ ሌላ ...

ውሉን ለመለወጥ በእንግሊዞች የተሰጠ ናታ /ሚሞራንደም ወይም ደብዳቤ/ ለጃንሆይ አቅርቤ ሃሳቡን ተተስማመበት በኋላ ለእንግሊዞች ውሉን ለመለወጥ ኔጎሲየሽን ለማድረግ መፈለጋችንን

ስነግራቸው የሚደነግጡ መሆኑን ስለታወቀኝ፣ እኔ በውሉ መሠረት የሦስት ወር ፕሪየር ዋርኒንግ የሚሆን ኖታ ጻፍኩላቸው። በውሉ መሠረት እስከ ሦስት ወር ንግግር ካልጀመርን ውሉ እንዲፈርስና ማናቸውንም የያዙት ሁሉ እንደምንይዝ በጥብቅ አስታወቅሁ። ኬንያ ያላቸውን ጦር አሰርት አደረጉ። ተብዙ ክርክር በኋላ ንግግር ለማድረግ መልክተኛ መላካቸውን አስታወቁ።

ተእንግሊዞች ጋር ለተደረገው ኔጎሳሲዮን፣ በሎርድ ደላዋር የሚመራ 15 የሚሆኑ የእንግሊዝ መልክተኞች አዲስ አበባ ደረሱ። የኛ ደሌጌሽን የሚመራው በቢትወደድ መኰንን ሆኖ ተኔ ጋር እነ ጀኔራል ዐብይ፣ አቶ ወልደጊዮርጊስ፣ አቶ ይልማ፣ አቶ መኰንን ደስታ ነበሩ። ንግግሩ የሚካሄደው በሎርድ ደላዋርና በኔ መካከል ነበር። የሁለቱ መንግሥት ፓር ተ ፓርል ሆነን /ፕሮሲቬርባሉን ማየት።

ማናቸውም እንቀጽ፣ የኢትዮጵያን ነጻነት የሚነካ፣ ብዙ ችግር ሳይኖር ለመለወጥ ተስማማን፤ ሦስት ጉዳይ ላይ ብቻ ችግርና ኮንፍሊክት ደረሰ። እነኝህም፣

## ሀ. የኦጋዴን

ሎርድ ደላዋር ኦጋዴን ለኢትዮጵያ አይመለስም፤ ምክንያቱም ተአሜሪካኖች፣ መስኮብ፣ ፈረንሳይ ጋር እንግሊዝ ስምምነት አድርጋለች ሲል ተሟገተ። ስምምነቱም «ጦርነቱ ሲያልቅ ኦጋዴንና የጣልያን፣ የእንግሊዝ፣ የፈረንሳይን ሱማሌ አንድ ጋ ቀላቅለን በእንግሊዝ ውስጥ በኮሚኒ ወልዝ ለማስተዳደር ነው» አለ። እኔም «ኢትዮጵያ መጀመሪያዋ የፋሽስት ቪክትም ሆናና መጀመሪያ በድል ነጻ የወጣችውን፣ እናንተ የኛ አላይ /ቃል ኪዳን/ የሆናችሁት ኢትዮጵያን ለመከፋፈል አስባችሁን እንደሁ መቼም አንቀበልም። ለዚህም ጥብቅ ፕሮቴስት አደርጋለሁ» ብዬ፣ ወጣሁ። ወዲያውኑ ደህና ሆኖ የተሰናዳ ስምንት ገጽ የሚሆን የፕሮቴስታስዩን ደብዳቤ አሰናድቼ ማታውኑ ላኩለት። ኮፒም ለመስኮብ መንግሥት እንዲሁም ለአሜሪካንና ለፈረንሳይ መንግሥት አድርጌ እኔው እራሴ ወስጄ ማታውኑ አስረከብኩ፣ ለአምባሳደሮቹ። ይህም ሲደርሰው ሎርድ ደላዋር እንደ እብድ ሆነ። ይኸውም ለአሜሪካን፣

መስኮብ፣ ፈረንሳይ ጉዳዩ ስለተገለጠበት ነው። ለኛንሆ ይም ይህ ወረቀት ዊዝድሮው ታልሆነ ወደ አገሩ መመለሱን አስታወቀ። ጉባኤውም ለሦስት ቀን ተቋርጦ አብድ፣ ክሬዚ ሆነ። እኔም ወረቀቱን መልሼ አልወስድም ብዬ ጠነከርኩ። ብዙ ችግርም ሆነ። በውስጣችን ወረቀቱ ተመልሶ ይወሰድ የሚል ነበር። ይህን ተማድረግ እኔም ሥራውን መተው አስብኝ አልኩ። በዚህም የጠነከርኩበት ወደፊት ኡጋዴንን ወደእኛ ለመመለስ፣ የነሱን ግሬተር ሱማሌ ሃሳብ ለማጥፋት፣ እንዲሁም እንግሊዞችን በሌሎች መንግሥታት ፊት ማጋለጥ አስፈላጊ ሆኖ ስላየሁት ነው። ሦስት ቀን ከፈጀ ተብዙ ንግግር በኋላ እኔም ወረቀቱን ዊዝድረው ሳላደርግ ጉባዔው ተከፈተ፣ ኔጉሳሲዩን ቀጠለ፣ ዝርዝሩ ብዙ ስለሆነ ፕሮሲቬርባሉን ማየት ያስፈልጋል።

በመጨረሻም እንግሊዞችና ሌሎቹም አገሮች አሜሪካን ጭምር እኛም የነሱ አላይ እንደመሆናችን፣ ተጣልያን ጋር ገና የሰላም ውል ስላልፈረምንና በጦርነት ላይ ስለሆንን፣ ለጦሩ እንዲረዳ ጦርነቱ እስቲያልቅ ድረስ የኢትዮጵያ የገዥነት መብት እንደተጠበቀ ኡጋዴን በእንግሊዝ የጦር አስተዳደር ውስጥ እንድትቆይ በሚል ፎርማሊቲ ላይ ስምምነት ተደረገ። /As ally for the prosecution of the war, without prejudice of her sovereignty and until the end of the war, Ethiopia accepts to put Ogaden under the British military administration. ውሉን ማየት።/ ያንጊዜ ተማንም መንግሥት ጋር ግንኙነትም፣ በኤምባሲ ሬሌሽን የለንም። በእንግሊዞች እጅ ብቻ ነበርን።

## ለ. የባቡሩ ጉዳይ

ጦርነት ላይ ስላለን፣ እናንተም ባቡሩን ለማስኬድ ችሎታና ሰው ስለሌላችሁ፣ ለማስኬድ ችሎታ እስኪኖራችሁ ድረስ እንለቅም አሉ። እኛም ሰውም ቀጥረን ቢሆን እናስኬዳለን ብለን ተከራከርን። ባቡሩን በሚገባ ለማስኬድ ችሎታ ሲኖራችሁ፣ ይህም ሲረጋገጥ፣ ያኔ እንለቃለን አሉ። ባቡሩ ለጦሩ ይረዳል በማለት፣ አላይ እንደተባለው ምንም የተማረ ሰው ስለሌለ፣ ፈረንሳይም ተሸንፋ አገሩም በጀርመን እጅ ስለነበረ ተኋም

ጋር ለመሥራት ስለማይቻል፣ ሰው እስትናገኝ እነሱ እጅ እንዲቆይ ተስማማን።

## ሐ. በዓመት የሚሰጠን 12 ሚሊዮን ፓውንድ

እስታሁን ያለነው፣ በነሱ ገንዘብ እርዳታ ባመት 12 ሚሊዮን ፓውንድ ተጫ እየሰጡን ነበር። ገና በመቋቋም ላይ ነበርን፤ የልማትና የታክስም ጉዳይ ገና መጀመሩ ነበር። የኢትዮጵያ ገንዘብ መውጣት እላይ በተዘረዘረው መሠረት ላይ ነበር። የሚበልጠው የሚገበያየው በኢስት አፍሪካን ሽልንግ ነበር። «ገንዘቡን የምንሰጠው የምታወጡትንና የምትሠሩትን ሁሉ አንድ ኮሚቴ አቋቁመን እየተቆጣጠርን ነው፤ ያለዚያ አንሰጥም» አሉን። እኔም «ይህማ ፕሮቴክቴሽን ማለት ነው። ነጻ መንግሥት ሆነን ይህን አንቀበልም፤ ገንዘቡ ይቅርብን» ብዬ መልሼ የገንዘቡ ፋይት በዚሁ ቀረ። እንዳቅማችን ነጻነታችንን ይዘን ብንኖር ይሻላል ብዬ በዚህ ጃንሆይ በሙሉ ተስማሙበት።

## 4.4.1 የስምምነቱን ኢፌክት ለማስፈጸም የተደረገው ትግል

## ሀ. የባቡሩ ጉዳይ

ባቡሩን ለማስኬድ የውጭ ቴክኒሲያን መቅጠር አስፈላጊ ስለሆነ ዋይት ኮርፖሬሽን /White Corporation/ የሚባል የአሜሪካን ካምፓኒ፣ ድሮ ዓባይን ለማጥናት ጀምሮ ከነበረ ጋር ተስማማን። በወር ስድስት ሺህ ዶላር እየከፈልን፤ እሱም አዲስ አበባ መጥቶ ቢሮውን ከፈተ። ግን ወዲያውኑ ፈረንሳዮች በአሜሪካን ላይ ፕሬዥር ስላደረጉ አሜሪካኖች እምቢ ብለው ቢሮአቸውን አነሱ። የአሜሪካን መንግሥት ይህን ያስታወቀኝ በ1944 ሳንፍራንሲስኮ ለዩናይትድ ኔሽን ቻርተር ለማስናዳት ስሄድ ነው። በነንተ ምክንያት ተፈረንሳይ ጋር መጣላት አንፈልግም ብለው ቁርጥ እምቢታቸውን አስታወቁ። ተሴላም መንግሥት ጋር ሁሉ ጦርነት ላይ ስለሆን ግንኙነታችንም ኢምባሲ ሪሌሽን የለንም። በዚህም ምክንያት ተየትም እርዳታ ልናገኝ አልቻልንም።

በዚህም እኳኋን ባቡሩም የሚበልጠው 80 እጅ የፈረንሳይ ንብረት ስለሆነ ተነሱ ጋር ንግግር ማድረግ ግድ ሆነብን።

በባቡሩ ተውሉ ውጭ የጣልያን ወታደር ወደ ኢትዮጵያ እስገብቷችኋል በማለት ተአጼ ምኒልክ ጋር የተዋዋላችሁት ውል አደፈጋምና ሌላ ውል እንዋዋል፤ እስዚያ ባቡሩን አትረከቡም በማለት አንድ የውል ስምምነት አቀረብኩላቸው። እነሱም ወታደርም አላመጣን፤ ውሉንም አንሰውጥም ብለው ግትር አርገው ያዙ። እንደዚሁ በክርክር ቆይተን በ1946 ሉንዶን የሄድኩ ጊዜ መሲዩ ዜይ፤ የፈረንሳይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ እንድንገናኝ ጠይቀውኝ ያቀረብኩውን የፕሮቶኮል ውል እንቀበላለን አሉኝ። በዚህም አኳኋን አዲስ አበባ ስመለስ ውሉን ተአምባሳደሩ ጋር ፈረምን። ባቡሩንም ተእንግሊዞች ተረክበን ማስኬድ ጀመርን። ተትንሽ ዓመታት በኋላም አሁን ያለውን ውል ለመስማማት ቻልን። ይኸውም ባለቤትነቱ በግማሽ የኢትዮጵያ፤ በግማሽ የፈረንሳይ፤ የሥራ አስኪያጆቹና የቦርድ አባሎቹ እንዲሁ በግማሽ ኢትዮጵያና ፈረንሳይ፤ የባቡሩ ሄድኳርተር ፓሪስ መሆኑ ቀርቶ አዲስ አበባ እንዲሆን፤ የምናወጣውን ሕግ ሁሉ እንዲቀበል ሆኖ ነው።

## ለ. የኡጋዴንና የሬዘርቭድ ኤርያ አመላለስ

ይህንን አገር ለመመለስ ረጅምና አስቸጋሪ ትግል ተደርጓል /በሙሉ ፕሮሲቨርባሉም ማየት ይጠቅማል።/ በ1946 እ.ኤ.አ. ሉንዶን ሄጄ ተሚስተር ቤቪን ጋር /የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር/ ስለዚሁ ጉዳይ ንግግር ስናደርግ፤ «ኡጋዴንን እንለቅም፤ ምክንያቱም አስተዳድራችሁት አታውቁም፤ ይህን ቤት የሚሞላ የፍሮንቲየር ኢንሲደንት ያደረጋችሁት» አሉኝ። «ተሌሎች አገሮች ጋር ተነጋግረን የእንግሊዝ ሱማሌን፤ የጣልያንን ሱማሌ፤ አሁን በእንግሊዝ እጅ ያለውን እንዲሁም ኡጋዴንን 'ትልቋ ሱማሌ' ብለን እኛ ጋ ቀላቅለን ለማስተዳደር ሃሳብ አለን። ይህንንም ተትንሽ ወር በኋላ ለሚከፈተው ለሰላም ጉባኤ ልናቀርብ ነው» አሉኝ። እኔም፤ «ተጣልያን ጋር የተዋጋነው በኡጋዴን ነው። ይህን ሃሳብ ለማስፈጸም እንግሊዝ ኢትዮጵያን እንደ ጣልያን መውጋት አለባት። ሳንዋጋና ሳንሸነፍ ልትወስዱት አትችሉም» ብዬ፤ ተቆጥቼ ወጣሁ /ተኔ ጋር አቶ ተፈራ ወርቅና ጸሐፊ ትእዛዝ ነበሩ/። ወደዚያም ሄጄ ለምስችፍ ማስታወሻና ካርታ ጨምሬ ቤቪን

ያሰቡትን ሁሉ አስረዳሁት። እንግሊዞች ተኢትዮጵያ 1/3ኛ የሚሆን አገር ሊነጥቁን አቅደዋል አልኩት። እሱም አገሩ ሲገባ ፕሬስ ኮንፈረንስ አርጐ፣ «ይኸው እነኚህ ኮሎኒያሊስቶች የኢትዮጵያን ሩብ መሬት ሊነጥቁት ነው። እኛ ግን እንቃወማለን» ብሎ፣ አስታወቀ። ያንጊዜ እንግሊዞችና አሜሪካኖች፣ መስኩብ ቱርክንና ኢራንን አታክ አርጐ አገር ይወስዳል በማለት ይሰጉ ነበርና፣ ይህንን ሰበብ አርጐ አሳቡን እንዳይፈጽም በእንግሊዝ አገር ታላቅ ስሜት ደረሰ። በሐውስ ኦፍ ኮመንስ ስብሰባ ተደረገ። ቢቭ ተጠየቀ፣ በአጥፊነት። እሱም፣ «እነኚህ ሕዝቦች አሳዝነውኝ ነው፣ ግን ማንኛውንም ኢትዮጵያ ሳትስማማ ለማድረግ አላሰብኩም ነበር» ብሎ መለሰ።

ኢትዮጵያ አለመስማማቷ የታወቀ ስለሆነ ተብዙ ጭቅጭቅ በኋላ ኡጋዴንን፣ ተሬዘርቭድ ኤርያ በቀር፣ በ1948 እንግሊዞች ለኢትዮጵያ መለሱ። ሲመልሱም በኡጋዴናች ሽብር ሁሉ እንዲነሳ አቅደው ነበር። የጸጥታ አላፊውን ኮሎኔል ክፍሌ እና ሌሎችንም ልከን በጥንቃቄ ለመረከብ ቻልን።

**ሪዘርቭድ ኤርያ** /የግጦሹ ሥፍራ/ «እሱን መቼም ቢሆን አንመልስም፣ የእንግሊዝ ሱማሌ ከብት መጋጫ ነው። ይህ ወደ ኢትዮጵያ ተተመለሰ መቼም ሰላም አይገኝ» እያሉ እምቢ አሉን። እኛም «ብዙ ዓመታት ሙሉ በሰላም ኖረናል፣ የምትበጠብጡት እናንተ ናችሁ። በአጼ ምኒልክ ውል መሠረት እንደዚሁም በ1944 ስምምነት መሠረት አገሩን መልሱ» እያልን ተከራክርን፣ አንድ ትልቅ ደሊጌሽን አዲስ አበባ ልከው፣ "የቸርችል ካቢኔ በዚህ ቆርጦአል፣ መቸም ቢሆን አንመልስ» አሉ። እኔም ጉባዔውን ጥዬ ወጣሁ። ተተመለስኩ በኋላ በአምባሳደራችን አበበ ረታ በኩል ሪዘርብድ ኤርያን ለመመለስ ንግግር ታላደረግን ጉዳዩን ለሴኩሪቲ ካውንስል ማቅረቤን አስታወቅሁ። በኋላም በግድ ኔጎሳሲዮን ከፈቱ። በየምክንያቱ ሲጐተት ቆየ /ፕሮሲቨርባል/። በመጨረሻም ንግግሩን ሎንዶን ጃንሆይ ሲሄዱ /የመጀመሪያ ጊዜ/ እዚያ እንቀጥል አሉ። እኔም፣ «የእናንተ እንግዳ ሆነን እዚያ መነጋገር አልፈልግም» አልኩ። «እምቢ ታልክ ለብዙ ወራት ይቆያል» ብለው፣ አስታወቁ። ጉዳዩ ተሥፍራው እያልፍም ብዬ ተቀበልኩ። ጃንሆይ

በመርከብ ሲሄዱ እኔ እዚህ ንግግሩን ስቀጥል ቆይቼ በኋላ በአውሮፕላን አንድ ቀን ቀድሜ ደረስኩ። እዚያም ጃንሆይ ጉብኙቱን ሲያከናውኑ፣ ሚስተር ኤደንና እኔ ንግግሩን ቀጠልን፤ በመጨረሻም ስምምነት ደረስን። ይኸውም ባንድ ወር ውስጥ አገሩን ሲያስረክቡ ነበር። አዲስ አበባ ስንመለስ ተኤደን አንድ ቴሌግራም ለጃንሆይ ተላከ። የሚለውም፣ «አገሩ የተመለሰ ጊዜ ሕዝቡ ስለሚነሳ፣ ስምምነቱ ሥራ ላይ መዋሉ እንዲቆይ» የሚል ነበር። እኛም በውሉ መፈጸም አሰበት ብለን እምቢ አልን። ለሚደርሰው ኮንስኮንስ ኢትዮጵያ ኃላፊ መሆንዋን አስታውቀው በተባለው ጊዜ አስረከቡ። እኛም ብዙ ጥንቃቄ ወስደን ነበር። ወዲያውኑ በነሱ አነሳሽነትና ስለእኛ ፋንታ ታንድ ግሩፕ ወደ ዩናይትድ ኔሽን ቴሌግራም አስደረጉ። ተሕዝቡም ውስጥ መርጠው የገዟቸውን ወደ ጉባዔው ላኩ። ላቤቱታ እኔም ሄድኩ። ተሌሎቹ መንግሥታትና ተዋና ጸሐፊውም ጋር በመነጋገር ጉዳዩ የውስጣችን እንደመሆኑ መጠን ነገሩ በአጀንዳና በሌላም አኳኋን እንዳይነሳ ለማድረግ ቻልኩ።

## 4.2 የዩናይትድ ኔሽንን ቻርተር ለማሰናዳትና ድርጅቱን ለማቋቋም እንዲሁም ለመፈረም ያደረግነው

በጀኔቭ ማ በር ፋንታ ሌላ ማ በር መቋቋሙ እንደተሰማ እንደድሮው በልመና ተመግባት መሥራች አባል ለመሆን አሁኑኑ መድከም እንዳለብን ተረድቼው ነበር።

በ1944 /እ.ኤ.አ./ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለጃንሆይ አውሮፕላን ልከው፣ በሚስጥር ከመርከብ ላይ /ፖርት ሰይድ/ ጃንሆይና ሩዝቬልት ተገናኝተው ረጅም ንግግር ተደርጐ ነበር፤ እኔም አብሬ ሄጄ ነበር። ሌሎችም ራስ ካሣ፣ አቶ ይልማ ደሬሳ፣ ጀነራል መርድ [ረዳት] ነበሩ። በዚያን ጊዜም ወደፊት ለሚቋቋመው ማ በር መስራችና አባል እንድንሆን ጠይቀን ነበር። እሱም ቃሉን ሰጥቶን ነበር። እንደዚሁም በኤርትራ ላይ ያለንን ሬቨንድኪሺንና ተጣልያን የምንጠይቀውን ሁሉ በሚዘረዝር ማስታወሻ አቅርበን ነበር።

ተሩዝቬልት ጋር መገናኘታችን ሲሰማ ቸርችልም ተጃንሆይ ለመገናኘት መፈለጉን ጽፎ በሩዝቬልት እጅ ወረቀት ልኮልን ነበር።

/ተያልታ ጉባዔ ሲመስሱ ነው።/ ጃንሆይም ተቀብለው መነጋገሩን ፈቀዱ፤ በንግግሩም ጊዜ ሚስተር ኤደን ነበር። ለሩዝቬልት እንደሰጠነው አይነት በኤርትራ ላይ ያለንን ጥያቄና ተጣልያን የምንጠይቀውን የጦር ካሣ ለእነሱም ሰጠን፤ ሚስተር ኤደን ሃሳቡን ሁሉ ተቃወሙ። «ጣልያኖች ብዙ መንገድና ሌላም ሠርተውላችዋል፤ ይህ እንደ ካሣ ይቆጠራል፤ ምንም መጠየቅ አይገባችሁም» አሉን። ሁሉንም በማፈዝ እኳኋን ነበር የሚቀበሉው፤ ስምምነት ሳናደርግ ተለያየን።

የሳንፍራንሲስኮ ጉባዔ እንደተቃረበ እንደሌሎቹ ነፃ መንግሥቶችና አላይ የሆኑት ጥሪ ተደረገልን /በአሜሪካን ድጋፍ ነው ለማለት ይቻላል/። ተአፍሪካ ሦስት መንግሥቶች ብቻ ነበሩ /ኢትዮጵያ፤ ሊቤሪያና ግብጽ።/ ተእስያ ማንም የለም፤ ሕንድም ገና ነፃ አልወጣችም ነበር። የስብሰባው ተካፋዮች በጠቅላላው ወደ 52 መንግሥታት ነበሩ።

የኛ ዴሊጌሽን የሚመራው በቢትወደድ መኰንን ነበር። እኔ ምክትል ሄድ ኦፍ ደሊጌሽን ነበርኩ። ሌሎቹ ብላታ ኤፍሬም፤ አቶ አማኑኤል፤ አቶ አምባዬ፤ አቶ ምናሴና አቶ ጴጥሮስ ነበርን። ቢትወደድ መኰንን የቋንቋም፤ ሌላም ችግር ስላገኛቸው ወዲያው ተመለሱ። እኔም ሄድ ኦፍ ዲሊጌሽን ሆኜ ሥራው ተጀመረ /ግንቦት 1944/።

በሥራውም ጊዜ የኢትዮጵያ ደሊጌሽን ብዙ አመንድመንት እያቀረበ ለጉባዔው ኮንትሪቢውሽን አድርጓል። /ፕሮሲቨርባል ማየት፤ የዩናይትድ ኔሽን ዶክመንት።/ እኔም ተጣልያን ጋር ባለን ኤክስፒሪያንስ እየጠቀስኩ ብዙ ኢንተርቬንሺን አደርግ ነበር። አንዱ በምሳሌ ያስቀበልነው፤ «አንድ መንግሥት አንድ ሌላ ሀይል ሲያጠቃኝ ይሰናዳል ብሎ አቤት ባለ ጊዜያት ሴኩውሪቲ ካውንስል መሰብሰብ አለበት» ብዬ አቅርቤ ነበር። አሜሪካኖች ይህን ሃሳብ በሆን ባልሆነው እውነቱ ሳይረጋገጥ መሰብሰብ የለበትም ብለው በብርቱ ተቃውመው ነበር። እኔም «ሰባት ወር ሙሉ ጣልያን ሊወጋን ነው እያልን ጀኔቭ አቤቱታችንን የሚሰማው ጠፍቶ፤ ጣልያን ጦሩን መድፉንና ታንኩን በሬድሲ ለማጋዝ ጊዜ ተሰጥቶት፤ በኋላ ሰላሳ ኪሎ ሜትር ኢትዮጵያ ውስጥ ከገባ በኋላ ነው አቤቱታችንን ለማየት የተቀበሉት። በክርክሩም ጊዜ ጣልያን እኛን ለመውረር ቻለ» እያልኩ አስረዳሁ። ብዙ መንግሥቶች ይልቁንም ፈረንሳዮች በዚህ

ኢምፕሬስ ሆነው አመንድማውን ተቀበሉት፡፡ በዚህ ምክንያት ነው አሁን ማንም መንግሥት አቤት ሲል በየጊዜው ሲኩውሪቲ ካውንስል የሚሰበሰበው፡፡ ታንድ ወር በኋላ ሥራው አለቀና በቻርተሩ ላይ የሃምሳ ሁለት ሄድ ኦፍ ዴሊጌሽን ዲክሌራሲዩን እያደረጉ በየተራ ፈረሙ፡፡ እኔም በተራዬ በኢትዮጵያ ስም በፊርማዬን ዲክላራሲዮን አደረግሁ፡፡ ስፈርም የተነሳው ፎቶግራፍና ዲክላራሲዩን አርካይቭ ይገኛል፡፡

ተሳንፍራንሲስኮ ስመለስ ዋሽንግተን ሄጄ ከአሜሪካን መንግሥት ጋር ልዩ ልዩ ንግግር አደረግሁ /የተቀመጥኩትም ብሌር ሃውስ ነበር/፡፡ ተኔ ጋር አቶ ምናሴ ነበሩ፡፡ በዚያም ጊዜ ዋና የፈጸምኩት የኢትዮጵያን ኤይርላይንስን ማቋቋም ጉዳይ ነው፡፡ ዝርዝሩ ብዙ ነው /ፕሮሲቨርባል ማየት ያስፈልጋል/፡፡ ባጭሩ ያንጊዜ ፓይለትም፣ አውሮፕላንም ስለሌለን አሜሪካኖችና እኛ በማ በር አንድ ኤርላይንስ እናቋቁም ብዬ ጠይቄ ነበር፡፡ እነሱ ይህን አንድም ኢትዮጵያዊ አውሮፕላን ላይ አይወጣም በማለት አልተቀበሉትም፡፡ በኋላም አዲስ አበባ መጥቼና ተጃንሆይ ተመካክሬ እኛ ራሳችን እናቁም፣ አውሮፕላኑን በክሬዲት ይሽጡልን፣ ማኔጅመንትም በዓመት የተወሰነ ገንዘብ እየከፈልን ያግዙን የሚል ሀሣብ ላይ ደረስን፡፡ ይህን ሀሣብ ይዤ ሄጄ ከደብልቢ /T.W.A./ ተነጋገርን፣ በዚህ ስምምነት ለማድረግ ቻልኩ፡፡ ተT.W.A. ፕሬዚዳንት ጋር ውሉን በአዲስ አበባ ተፈራረምን /ዝርዝሩን ማየት/፡፡ ተዚያም በኋላ ኢትዮጵያን ኤርላይንስ ተቋቋመ፡፡ አሁን በኛ ፓይለትና ማኔጅመንት የሚካሄደው፣ በዓለምም ታላቅ ስሜት ያለው የኢትዮጵያ ኤርላይንስ ያንጊዜ ብዙ የደከምኩበት መሆኑን አርካይቭ ያስረዳል፡፡

## 5. የሰላም ጉባኤ /Peace Conference/ ተጣልያን ጋር /ሰኔ—ሐምሌ1946 እ.ኤ.አ./

ተ1943 ጀምሮ ወደፊት የዓለም ጦርነት ታለቀ በኋላ በሚደረገው የሰላም ጉባዔ ተካፋይ እንዳንሆን ጠላቶቻችን እንዳያደርጉ ሥጋት ነበረን። ይኸውም በዓለም ጦርነት ፓርቲሲፔት አላደረጉም በማለት፣ የኛ ጦርነት የተጀመረውና ያለቀው በ1936 እንደመሆኑና የሚበልጡት አገሮች የጣልያንን ይዞታ ስላወቁ፣ ይህንን ሁሉ በማሰብ ተጣልያን ጋር ጦርነቱ እንዳለቀ ወታደር ልከን እኛም አብረን ከባለቃልኪዳን አገሮች ጋር ተሰልፈን ጣልያንን ተኢትዮጵያ ውጭ እንድንዋጋ ፕሮፖዛል እየደጋገምን አቅርበን በፍጹም አልተቀበል አሉን /ሰበቡ የሰለጠነ ወታደር የላችሁም ነበር/።

ተጣልያን ጋር የሚደረገውን የሰላም ውል ድርድር አድርገው አሜሪካን፣ ሞስኮብ፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይና ቻይና ሲነጋገሩ በዚሁ ጉባዔ ተካፋይ የሚሆኑትን መንግሥት፣ ቁጥርና ዓይነት ወሰኑ። የሰላም ውል የሚደረገው ከጣልያን ጋር በ1940 የተጀመረውን ጦርነት ለመዝጋት መሆኑንና ተካፋይ የሚሆነውም አገር በውጊያው ሥፍራ በአውሮፓ ጦር ልኮ የተዋጋ መሆኑን አስታወቁ።

በዚህ አኳኋን ተባለቃል ጓደኞች ተምንላቸው ጋር ተጣልያን ጋር ለሚያደርጉት የሰላም ውል ተካፋይ ለመሆን ሳንችል ነው። ታላቅ ጉዳትም ሊያመጣብን መቻሉን ገመትሁ። ለድርድር ጣልያንን ብቻችንን የገጠምን ጊዜ ጥያቄያችንን ሁሉ በእምቢታ እንደምትመልሰው አይጠረጠርም።

ስለዚህ ታራቶቹ ታላላቅ መንግሥቶች አሜሪካ፣ መስኮብ፣ እንግሊዝና ፈረንሳይ ጋር ንግግር ጀመርኩ። በመጀመሪያ ተአሜሪካኖች ጋር፣ ተዚያ ጊዜ ጀምሮ ለኛ ሲምፓቲ ያላቸው እነሱ ነበሩ። ለነሱም አንድ ደህና አድርጌ የጻፍኩትን ሚሞራንደም አቀረብኩላቸው።

ሀ/ እኛ ተጣልያን ጋር ገና በጦርነት ላይ እንዳለንና አርሚስቲስም፣ የሰላም ውልም እንዳልፈረምን /ፈረንሳይ ተጀርመን ጋር አርሚስቲስ ሲፈርም እንኳ፣ን/፣

ለ/ እምስቱን ዓመት ሙሉ እንያገዘም በማለት አርበኞቻችን በመዋጋታቸውና ጃንሆይም በጀኔቭ መሟገታቸውን ስለቀጠሉ /ማንኛውንም ተጣልያን የቀረበውን እፈር እምቢ ብለው፣ ጣልያን በኢትዮጵያ ከተማዎችን ተመያዙ በቀር አገሩን እንዳልያዘው፣

ሐ/ እኛ ውጊያችንን ባንቀጥል ኖሮ ጣልያን ኢትዮጵያ ላይ ብዙ ሰውና ወታደር አስፍሮ፣ ኢትዮጵያን እንዳንድ ቤዝ ፎርትሬስ አድርጐ ሱዳንና ግብጽን እንዲሁም ኬንያን በቀላሉ ይይዝ ነበር፣

መ/ ይህ ስላልሆነ ነው በ1940 ገና ጣልያን ጦር ሲገባ በትንሽ በኢትዮጵያ አርበኞችና በትንሽ እንግሊዝ ወታደር ወዲያውኑ እጁን የሰጠው።

ሠ/ ስለዚህ እኛ በ1940 ለተጀመረው ጦርነት ጦር ሜዳ ላይ ወታደር ልከን እንደተዋጋን መቆጠር አለበት፣ በዚህ ሁሉ ምክንያት ለሰላሙ ጉባዔ ተካፋይ መሆን እንዳለብን በማለት ነበር።

አሜሪካኖችም ሀሳቡን በሲምፓቲ ተቀብለውት «እኛ እንቃወምም፣ ሃሳቡን ያመጣውና ብዙህ ያስቸገረው መስኮብ ስለሆነ እሱን ታስቀብላችሁ እኛ እንቀበላለን» አሉኝ። /መስኮብ ይህን ያመጣው አገር የበዛ ጊዜ የሚበልጠው የዌስት ወገን ስለሆነ በድምጽ ብልጫ እንዳይሸነፍ ነው።/

ተመስኮብም ጋር ንግግር አደረግሁ። «እኛ መጀመሪያ የፋሺስት ቪክትም ሆነን፣ አሁን እኛን የወጋው ፋሽስት አገር ጋር የሰላም ውል ሲደረግ እንዴት እኛ ተካፋይ አልሆንም? መስኮብስ የአፍሪካና የቲኒኒሽ አገሮች ተከራካሪ አይደለምን? የኢትዮጵያና የመስኮብ ወዳጅነት በታሪክ ውስጥ እንዴት ይረሳል? ጀኔቭስ ጉባዔ ላይ እናንተ አልነበራችሁም ለኛ የምትከራከሩት?» በማለት። መስኮብ ሁሉንም ታመዘበ በኋላ እደግፋለሁ ብሎ ቃል ሰጠ። ተዚያም በኋላ ሁለቱ ታላላቅ መንግሥቶች ተተቀበሉት በኋላ ፈረንሳይንና እንግሊዝን ለማስቀበል በሚገባቸው መንገድ አስረድቼ እንዲቀበሉት አደረግሁ። በዚህ አኳኋን ነው እስቸጋሪና ደልኬት በሆነ ኔጐሳሲዮን ኢትዮጵያ ተሌሎቹ ሃያ መንግሥታት ጋር ተሰልፋ ተጣልያን ጋር ለሚደረገው የሰላም ውል ተካፋይና ጥያቄዎችን ሁሉ ለማቅረብ የቻለችው።

ለሰላሙ ጉባዔ የሚቀርበውን ኢሴ ሁሉ ማስናዳት ነበረብኝ።

ሀ/ ጣልያን በቅኝ አገሮች ላይ ያላትን ይዞታ ሁሉ እንድትለቅ ማድረግ፤

ለ/ በኤርትራ ላይ /እንዲሁም በሱማሌ ላይ/ ያለንን ሬቪንዲክሽን ማስናዳት፤

ሐ/ የጦር ካሣ መጠየቅና የተደረገብንን ጥፋት ዝርዝር ማስናዳት/ የሞተውን ሰው ቁጥር፤ የተቃጠለውን ቤትና ቤተክርስቲያን/ ሌላም የደረሰ ጉዳት፤ ይህ ሁሉ ብዙ ሪሰርች ያስፈልጋል። እስታቲስቲክ የለም፤ የተማረ ሰው የለም።

ተሃያ መንግሥታት፤ ተካፋይ ተሆኑት፤ ለሁለት ወገን ስለለዩ ተማን ጋር ይጠቅመናል። ተሃያዎቹ 16 የዌስት ወገን ስለሆኑ ጣልያንን ይረዳሉ፤ ጣልያን ኮሚኒስት እንዳትሆን። ከአስራ ስድስቶቹ ውስጥ እነአሜሪካን፤ እነእንግሊዝና ፈረንሳይ የሚገኙበት ነው። አራቶቹ ደግሞ መስኮብ፤ ዩጉዝላቪ፤ ኡክሬንና ቢሉፕሽያ ጣልያንን ይቃወማሉ። ከመስኮቦች ጋር የሆን ከ16ቶቹ በድምጽ ብልጫ ያሸንፉናል፤ ተነሱ ጋር የሆን ጊዜ ጣልያንን ለማስቀየም ስለማይፈልጉ ብዙ አይረዱንም በማለት ታላቅ ሥጋት ላይ ወደቅን።

በዚህም ምክንያት ለዋናቹ አሜሪካን፤ እንግሊዝ፤ መስኮብና ፈረንሳይ በየጊዜው የኛን ጥያቄና ሐሳብ እንዲረዱት በየጊዜው እደክም ነበር። ይህም ተ1944 ጀምሮ ሩዝቬልትንና ቸርችልን ከተገናኘንበት ጆምሮ።

የጉባዔው ጊዜያት እንደደረሰ ተአራቶቹ በፓሪስ ለሚደረገው የሰላም ጉባኤ ተካፋይ እንድንሆን ሌሎቹ መንግሥቶች እንደተደረገው ጥሪ ደረሰን። እኔም እውጭ አገር ይኸንኑ ለመነጋገር ስለነበርኩ ለጃንሆይ ሥራውን እሠራለሁ ግን በዛ ያሉና ታላላቅ ሰዎች እንደን ቢትወደድ መኮንንና ራስ አበበ ተጨምረው እንዲላኩ ብዬ አሳሰብኩ። /እነሱን አንቀበልም በማለት የሳንፍራንሲስኮ ጉባዔ ኤክስፒሪያንስ ስላለ/ የደሊጊሽኑ መሪ እኔ ሆኜ ተኔ ጋር እነ ብላቴን ጌታ ሎሬንዞ፤ ብላታ ኤፍሬም፤ አቶ ተፈራወርቅ ኪዳንወልድ፤ አቶ ተስፋዬ ተገኝ፤ አቶ መንበረ ያየህይራድ ሆነን የጉባዔው ተካፋይ እንድንሆን ጃንሆይ ትእዛዝ በብእራቸው ጽፈው ላኩልኝ /ታደራ ጋር/፤ ይህ ደብዳቤ አርካይቭ ይገኛል።

## 5.1 ኮንፍራንሱና ዲቤቱ እንደምን እንደተካሄደ

በየተራ መልክተኞች ሁሉ ሃሳባቸውን ለመግለጽ ዲስኩራቸውን አደረጉ። እኔም የኢትዮጵያን ፖዚሽን፤ የተደረገባትን ግፍና ጉዳት፤ ጥያቄያችንና ሪቬንዲክሽናችንን ያጠቃለለ ትልቅ ዲስኩር አደረግሁ /ዲስኩሩን ማየት/።

በመጨረሻም የኢጣልያን ተራ ሲደርስ አስጊ ኢንሲዳ /incident/ ደረሰ። ይኸውም የጣልያን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ጋስፓር በዲስኩሩ ውስጥ፤ «እዚህ የተሰበሰብነው የውሉ ድራፍት እንደሚያመለክተው በ1940 ዓ.ም. የተጀመረውን ጦር ለመዝጋት ነው። (... to put an end to the 1940 war ...) ተኢትዮጵያ ጋር ጦርነቱ የተጀመረው በ1935 ሆኖ በ1936 አለቀ። ስለዚህ ኢትዮጵያ እዚህ ምን ታደርጋላችሁ? እዚህ ታላችሁት በዘጠና ፐርሰንት የእኛን ይዞታ አውቃችኋል። በዚህ አኳኋን ተሆን የቻይናና የጃፓንን ጦርነት ለምን አናይም?» ሲል ተናገረ። በመልክተኞቹ ላይ የመቸገርና የመደንገጥም መልክ ይታይ ነበር።

እኔም ወዲያውኑ መድረክ ጠይቄ በቁጣ መልክ ጠንካራ የሆነ መልስ ሰጠሁ። ይኸውም እንዲህ የሚል ነበር። «እኛ እዚህ የመጣነው ሰላምን ፈልገን ነበር፤ ተጣልያን ጋር በ1935 ጦርነቱ ተተጀመረ ጀምሮ እስታሁን በጦርነት ላይ ነን። አርሚስቲስም፤ ሰላምም ውል አላደረግንም። ጣልያን ሰላም አልፈልግም፤ ጦርነቱን እቀጥላለሁ ካለ ጦርነቱ እንዲቀጥል ዛሬውኑ አዲስ አበባ ለጃንሆይ ቴሌግራም አደርጋለሁ። በዚህ አኳኋን በኢትዮጵያ የሚገኙት ወደ 300,000 የሚሆኑ ጣልያኖች ለሚደርስባቸው ሁሉ እኛ ኃላፊ አንሆንም» አልኩ። ጉባዔው የበለጠ ችግር ላይ ሆነ፤ ለጊዜው እንዲቆም ተደረገ። እውጭ በአሜሪካና በፈረንሳይ አማካይነት ኔጎሳሲዮን ተደረገ። ሁሉም «አብዳችኋል?! ኢትዮጵያ ያሉት ጣልያኖች ሁሉ ያልቃሉ!» በማለት በጣልያኑ ላይ ወረዱበት። በመጨረሻም እሰላም ውል ውስጥ፤ «በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ትልቁ ጦርነት የተጀመረው ጥቅምት 3/1935 /ኢ.ኤ.አ/ ነው። ይህም ውል የሚያዘው ሁሉ ተዚያ ጀምሮ መርጋት አለበት» የሚል

ቃል እንዲገባ ጠየቅሁ። ይህም፣ ውል እንዲሁም ፕሮሚስ ሆኖ ጣልያን እንዲቀበል አደረጉት። ይህም በተፈረመው የሰላም ውል በአንቀጽ 38 ይገኛል።

## 5.1.1 ስለአገር ያደረግነው ሪቬንዲክሽን /ጥያቄ/

ታሪክንና ማስረጃን ጨምረን በሚገባ በኤርትራ ያለንን ጥያቄ አቀረብን፤ እንደዚሁም ታሪክን በመጥቀስ በሶማሌ ላይ። ጣልያን በቅኝ አገሮች ላይ ያላትን ይዞታ ሁሉ እንድትተው፤ ስለዚህም ያደረግነውን ዲስኩር፣ ያቀረብነውን ሜሞራንደም ሁሉ ማየት ስለዚህም ጉዳይ ፕሮፌሰር ቤንችዊች የጻፈውን ማየት።

የግብጽ መልክተኛ /ላንድ ጊዜ እንዲናገሩ ተፈቅዶላቸው ነበር/ «ድሮ ማሳዋን ይዘን ነበርና ለኛ ይገባል» ብሎ ጥያቄ አቅርቦ ነበር። የሚገባውን መልስ ሰጠሁት። «መጀመሪያ የቱርክ ተገዢዎች ነበራችሁ፤ የመጣውም ለትንሽ ጊዜ ትንሽ ሥፍራ ይዞ ወዲያው ተመለሰ። እናንተ ግን በነራስ አሉላ በዶጉላቲና ጉንዳጉንዲ ተዋርዳችሁ የተጨረሳችሁበትን አስታውሱ» ብዬ መለስኩለት። ተዚያም በኋላ በጥያቄም አልቀጠለም።

ጉባዔው ሁለት ወር ያህል ተሠራ፤ በኋላ ስለጣልያኖች ቅኝ ግዛቶች ቀጥሎ ባለው አኳኋን ተጻፈ።

አንቀጽ 23 ሀ/ ጣልያን በቅኝ አገሮች ላይ ያላትን መብት ሁሉ ለቃለች፤ ለ/ የነኝህ አገሮች እድል /fate/ በታላላቆቹ አራት መንግሥታት አሜሪካ፣ መስኮብ፣ እንግሊዝና ፈረንሳይ ይወስናል። ሲወስኑም የሕዝቡን ፍላጐት፣ የሰላምንና የሴኩሪቲን መሠረት ኢንትሬ ያላቸውንም መንግሥታት ሃሳብ በመስማት ነው። አራቶቹ ስምምነት ያላገኙ ጊዜ ጉዳዩ ወደ ዩናይትድ ኔሽን እንዲቀርብ የሚል ነው።



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ከፈረንሳይ ፕሬዚዳንት ቻርለስ ደጎል ጋር ሲወያዩ።

ባንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ በዚህ ድራፍት ላይ እኛ ብዙ ደክመናል። ሰላምና ሴኩሪቲን መሠረት በማድረግ ያልነው፣ እኛ በየጊዜው የተወረርነው በኤርትራና በሱማሌ በመሆኑ ኢንትሪ ያላቸውን መንግሥታት ሃሳብ ያልነው አራቱ ፊት እየቀረብን ሃሳባችንን እንድናቀርብ ነው።

የጦር ካሣ፣ አራቱ መንግሥታት ለኢትዮጵያና ለአልባኒ አምስት ሚሊዮን የአሜሪካን ዶላር እንዲከፈል ነበር ያቀረቡት።

ጣልያን ግን ለኢትዮጵያ ምንም መክፈል አይገባኝም ብሎ ተሟገተ። ለዚሁም የሠራውን መንገድ፣ መብራት፣ ቤት፣ ሌላም ልዩ ልዩ የሚያሳይ መጽሔት፣ በፊት ኢትዮጵያ ምን መንገድ፣ ምን መብራት፣ ምን ቤት እንዳላት /እንዲያስቅ እያደረጉ/፣ እነሱ ተመጡ በኋላም የተሠራውን መንገድ ሌላም የሚያሳይ ሥዕል ጨምረው

አቀረቡ፡፡ እኔም የተሠራው መንገድ ለስትራቴጂ ውጊያ የሚረዳ ጋራ ጋራውን እየተከተለ እንጂ ለልማት የሚሆን ሜዳ ሜዳውን ወይም ወንዝን እየተከተለ አለመሆኑን፣ ለራሳቸው ለውጊያ ጥቅም እንጂ ለኛ አይጠቅመንም ብዬ በሚገባ መልስ ሰጥቻቸው እነሱም ኢምፕሬስ ሆኑ፡፡ በመጨረሻም ተብዙ ክርክር በኋላ 25 ሚሊዮን የአሜሪካን ዶላር ተወሰነልን፡፡ /30 ሚሊዮን ሲሆን ሃሳብ ቀርቦ በአንድ ድምጽ ብቻ /ግሪክ ወደ አልባኒ/ ያው ሃያ አምስት ሚሊዮን ብቻ ሆነ፡፡

## 5.1.2 የጣልያን ንብረትና የጣልያን ኤምባሲ

በሕጉ መሠረት የሚወሰደው የጣልያን የመንግሥት ንብረት የሆነውን ብቻ ነበር፡፡ እንደዚሁም ኤምባሲ የተባለ ሁሉ አይነካም /ፈረንሳይ ለምሳሌ፣ እንደኛው አራት ዓመት በጀርመን ተይዛ ነፃ ስትሆን የጀርመን ኤምባሲና የጀርመኖች የግል ንብረት አልነካችም/፡፡ እኛ ግን ጣልያኖች የሠሩት የግል ቤትና ያፈሩትም ንብረት ባምስቱ ዓመት በውጊያ ላይ ስለሆነ በጉድ ፈዝ የተደረገ አይደለምና አይረጋላቸውም ብለን በዚሁ አስወሰንን፡፡ ኤምባሲያቸውንም እንመልስም ስንል ግን ሁሉም ጮሁብን፡፡ እኔ ግን ጣልያኖች የኤምባሲን ካራክተር አልጠበቁም፤ የጦር ሠፈር አድርገውት ነበር ብዬ ተሟገትሁ፡፡ በዚህም አኳኋን አሜሪካን፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይና መስኮብ ይህ ውል ውስጥ ተሚገባ አራታችን ኦፊሴል የሆነ ዴክሌሬሽን እናደርጋለን ብለው አደረጉ፡፡ ይህም ኤምባሲን የሚመለከተው አንቀጽ አይረጋም፤ ኢትዮጵያ ትውሰደው የሚል ነበር፡፡ በዚህ አኳኋን የኢጣልያንን ኤምባሲ ተረከብን፡፡ /በኋላ የተሰጣቸው በሱ ግምት ጣልያን አገር እነሱ ለኛ ቦታና ቤት ስለሰጡ ነው፤ አሁን የእኛ ኤምባሲ ያለበትን፡፡/

የወሰድነው የጠላት ንብረት በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠር ነው፡፡ የቆታም ዳም የተሠራው በተቀበልነው የጦር ካሣ መሆኑን ማስታወስ ያስፈልጋል፡፡

## ማጠቃለያ

1. እስላም ጉባዔ ተሴሎቹ መንግሥቶች ጋር በእኩልነት ተካፋይ ለመሆን ቻልን፤
2. ጣልያን በቅኝ አገሮች ላይ በኤርትራ፣ ሱማሌ፣ ሊቢያ ያላትን መብት እንድትሰቅ አድርገናል፤
3. በመጀመሪያ ጊዜ በኤርትራ ላይ ያለንን ጥያቄ በሚገባ ለማቅረብ ቻልን፤
4. የጣልያንና የኢትዮጵያ ጦርነት በ1940 የተጀመረው የዓለም ጦርነት አንዱ ክፍልና መጀመሪያው መሆኑን አስቀበልን፤
5. የጣልያን ቅኝ አገሮች ጉዳይ ሲወሰን የኢትዮጵያ ሃሳብ እንዲሰማና ኮንሲደሬሽን እንዲሰጠው አስቀበልን፤
6. 25 ሚሊዮን ዶላር የጦር ካሣ እንዲሰጠን አደረግን፤
7. የጠላት ንብረት፣ የመንግሥትም የግልም፣ ኢትዮጵያ እንድትወስድ አስደረግን።

# 6. ኤርትራን ለመመለስ ያደረግሁት ትግል

## 6.1 አራቶቹ መንግሥቶች ዘንድ የተደረገው ትግል

በፓሪስ የሰላም ውል ውስጥ /1937/ እንደተመለከተው አራቶቹ መንግሥታት /አሜሪካ፣ መስኮብ፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይ/ የጣልያንን የቅኝ አገሮች ጉዳይ መጨረስ ያለባቸው ባንድ ዓመት ውስጥ ነው። ሳይጨርሱ የቀሩ ጊዜ ጉዳዩ ለዩናይትድ ኔሽን እንዲቀርብ ነው የተወሰነው። ጉዳዩን ለመወሰን መሠረት የሚያደርጉትም እላይ ተዘርዝሯል። በዚህ በአንድ ዓመት ሥራዬ ጊዜያት የገጠመኝን እዚህ ለመዘርዘር አይቻልም።

ያራቱ መንግሥታት በሉንዶን ተሰብስበው የኢትዮጵያን ሃሳብ እኛ እንስማለንና በዚህች ቀን እንድትገኝ የሚል መልክት አርብ /ሁለት ቀን ሲቀረው/ አስታወቁ። ያን ጊዜ አውሮፕላን የለን፣ የእንግሊዝ /B.O.C./ የሚመጣው በሳምንት አንድ ቀን ነው። የትራንስፖርት ችግር ስላለብኝ ለአራትና ለአምስት ቀን እስተላልፉልኝ ብዬ ጠየቅሁ። እነሱም ባልነው ቀን ታልሆን ብለው ጥያቄዬን አልቀበል አሉ። ችግር ላይ ሆንን። አንድ ትንሽ አይሮፕላን፣ ለጃንሆይ የእንግሊዝ መንግሥት የሰጣቸው፣ እንሬጅስተርድ የሆነች፣ ይገኘ ለመሄድ ቆረጥሁ። በሱዳን፣ ግብጽ፣ ግሪክ፣ ፈረንሳይ አገር እያረፈች ቤንዚን በመውሰድ መንገዝ ስላለባት ተነኘህ አምባሳደሮች የተጻፈ ወረቀት ተቀብዬ ቅዳሚት ተነሳሁ። ሱዳን ደህና ተቀበሉን። ግብጽ ግን ሉክሶር ስንደርስ ወረቀቱን ባሳየውም «እኛ ተእስራኤል ጋር ጦርንት ላይ ነው ያለነው። ይህ ወረቀት እውንት መሆኑን አላውቅም፣ ፓይለቱም ነጭ ስለሆነ እስራኤል ይሆናል፣ ጦርንት ላይ ስለሆንም ታስር ሰዓት /4 afternoon/ በኋላ መብረር ክልክል ነው። ስለዚህ በቀጥታ ወደ ካይሮ ሄዳችሁ እዚያ ትመረመራላችሁ፣ በአውሮፕላን እናስከትላችኋለን» አለኝ። እሽ ብለን ተሳፈርን። ፓይለቱ ምን ላድርግ አለኝ። ካይሮ የሄድን ጊዜ ተሰኞ ቀጠሮ ሊሰናከልብኝና **የኢትዮጵያ ጉዳይ ሊበላሽ** ነው። ለፓይለቱ ገዞም

ብለህ ቀይ ባህርን እየተከተልክ ሂድ፣ ሪስክ ማድረግ አለብን አልኩት። በዚሁ ዝም ብለን እየሰጋን ተጓዝን። ሜዲትራኒያ ባህር ስንደርስ እፎይ አልን። ማታ በጭለማ በ3 ሰዓት ሼፒር ደረስን። ቤንዚን አለቀብን፣ እንድንወርድም ፈቃድ ጠየቅን። መብራት ስለሌላቸው የካሚዎን መብራት አብርተው ለመውረድ ቻልን። እዚያም አደርን። በማግሥቱ እሁድ ግሪክ ደረስን፣ ደህና ተቀበሉን። ወዲያው ተነስተን ፈረንሳይ አገር ማርሴይ አረፍን። ቤንዚንም ታልክፈላችሁ አንሰጥም ብለው ያልታወቀ አውሮፕላን ነው በማለትም አስቸገሩን። በእንደዚህ አኳኋን እንደምንም ሉንዶን ደረስን። ይህ አንዱ ምሳሌ ብቻ እንዲሆን ነው።

**እሉንዶን** እንደደረስሁ ያራቱን ወኪሎች እየዞርኩ ተገናኘሁ። እንደምንም በችግር እንደመጣሁ አስረዳኋቸው። ዋናው ኮንታክት ለማድረግ ነው።

ጉባዔውም እንደተከፈተ 60 ገጽ ያለውን ዲስኩሬን አትሜ ላራቶቹ ሰጥቼ ማንበብ ጀመርኩ። ጊዜያቱሙቀት ስለነበረ /August/ የፈረንሳይ ወኪል፣ «ይህንን ሁሉ እስክታነብ እዚህ ልንቆይ ነውን? ንግግርህን ታድለናል፣ ለምን ታነበዋለህ?» አለ። እኔ፣ «ተብዙ ችግር በኋላ ስንት ሺህ ኪሎ ሜትር አቋርጬ የመጣሁት ሁለት ሰዓት ትሰጡናላችሁ ብዬ ተስፋ በማድረግ ነው» አልኩት። ፕሬዝዳንቱ መስኮብ ስለነበረ /ማሊክ/ እውነቱን ነው፣ መስማት አለብን ብሎ ወሰነ። ንግግሬም ታለቀ በኋላ አንዳንድ ጥያቄ ሲደርስ ለሁሉም መለስኩ። የፈረንሳይ /ማሲግሊ/ «ስለኤርትራ ጥያቄ እንኳን ይሁን፣ ደግሞ ሱማሌ ምን መብት አላችሁ?» አለኝ። ዋሚ፣ «ታሪክ እንደሚያስረዳው የፈረንሳይ ሱማሌ የእኛ ነበር። ይህን አያውቁትም?» መስኮብ ደስ ብሎት ያውልህ መልስ አለው። ከዚያም በኋላ በደንብ የተሰናዳ ሜሞራንደም አስረክቤ ተለያየን።

ከዚህም በኋላ አራቶቹ መንግሥቶች በኤርትራና በሱማሌ የኢንኳየሪ ኮሚሽን ላኩ፣ የእንግሊዝ መልክተኛ /በኮሚስዮኑ ውስጥ/ ስታፎርድ ነበር፣ በፊት አዲስ የገንዘብ አማካሪ የነበረው። የአሜሪካኑ የሚመራው በሚስተር ኸተር ነበር፣ በስቱት ዲፓርትማ የኢትዮጵያን

ጉዳይ የሚከታተልና ተብዙ ጊዜ ጀምሮ የማውቀው። የፈረንሳይ ቢሻር ዳፎዚዬ የሚባለው፣ የመስኮብን አላውቀውም ነበር።

ኤርትራ፣ አሥመራ ሄድኳርተራቸውን አድርገው ኢንኳየሪውን በሚያደርጉበት ጊዜያት እኔ አሜሪካን አገር ለዩናይትድ ኔሽን ጉባዔ እገኝ ነበርኩ። ተኔም ጋር አቶ ገብረመስቀልና ብላታ ዳዊት ዕቁበእግዚእ ነበሩ። ኮሚሲዮኑ ኤርትራ በመገኘቱ ቸኩዬ በግብጽ በኩል ተመለስኩ። ከዚያም ኮሌራ ገብቶ ነበርና ለመከተብ የተወሰነውን ጊዜያት ግብጽ ተመድረሴ በፊት አላገኘሁም። አውሮፕላን ስጠብቅ ለሁለት ቀን ቆየሁ። ተዚያም አሥመራ ስደርስ አገረ ገዢው እንግሊዝ ኮሚስዮኑ ያለበትን ቻዎ የሚባለውን ሆቴል ሪኩዚስዮን አድርጉ ሥፍራው ሰውም አይገባም አለኝ። እኔ እዚያ አድሬ ተኮሚሲዮናቹ አባሎች ጋር ለመነጋገር ነበር /ስለማውቃቸው/። በኋላም አዲስ አበባ የሚመጣ የአሜሪካን አምባሳደር አንድ ሌሊት እዚህ ስለሚያድር እሱ እስኪመጣ ላንድ ሌሊት እዚያ እንዳድር ተፈቀደልኝ። እዚያም ተገባሁ በኋላ ማታውኑ እየመኝታ ቤታቸው ሄጄ እያንዳንዱን አባሎች አነጋገርኳቸው። ተስፋ የሚያስቆርጥ ነገር ነገሩኝ። የክርስቲያኑ ክፍል እንኳን እነራስ ተሰማ ተሰባ ሺህ ጦር ጋር ኢትዮጵያን አንፈልግም፣ እንግሊዝን ነው እንጂ ብለው ቃላቸውን ሰጥተዋል አሉኝ። በዚያን ጊዜ ሌአዞን ኦፊሰር ነበረን፣ እሱም ጀነራል ነጋ ኃይለሥላሴ ነበር። እሱንም በረጅሙ አነጋገርኩት። እንዳስረዳኝም የእንግሊዝ አድሚኒስትሬሽን ብዙ ሳቦታጅ እንዳደረገብን ነው፤ ትራንስፖርትና ቤንዚን በመከልከል። በዚህም ለሚስተር ቢቨን፣ የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣ ተገቢውን ፕሮቴስታስዮን በየጊዜው አደረግሁ። ችግሩ ምንም ትእዛዝ ቢሰጥ ኮሎኔል አፊክ ደግሞ የፈለገውን ያደርግ ነበረ። በመጨረሻም የኮሚስዮኑ ራፖር ታትሞ ለዩናቲድ ኔሽን ቀረበ። ስምምነት አላገኙም፣ አንዳንድ መንግሥት የራሱን ፖሊሲ ለኮሚስዮን አባል ላደረገው መሪ ትእዛዝ ስለሰጠው። ከኮሚሲዮኑ ራፖር ባጭሩ የሚለው /ትክክለኛውን ለማወቅ ራፖሩን ማየት ያስፈልጋል/ ቀጥሎ እንዳለው ነው።

ሀ/ አሜሪካንና እንግሊዝ ተሕዝቡ አርባ በመቶ ብቻ ተኢትዮጵያ ጋር ለመቀላቀል ይፈልጋል። /በ60 እጁ አይፈልግም።/ ስለዚህ

የአሜሪካን ሐሳብ ተእስመራ ከተማና ተምጽዋ በቀር አሰብና ሌላው የክርስቲያኑ አገር፣ አካለጉዛይ፣ ሀማሴን፣ ሠራዬና አቀርዳት ሳይጨመር፣ ለኢትዮጵያ እንዲሰጥ። የእንግሊዝ ሀሳብ ደግሞ ላስር ዓመታት ኤርትራን በሞግዚትነት ኢትዮጵያ እስተዳድራ ከዚያ በኋላ አገሩ ነጻ አገር እንዲሆን።

ሰ/ መስኮብና ፈረንሳይ ያቀረቡት ደግሞ ሕዝቡ ሰላሳ በመቶ ኢትዮጵያን ይፈልጋል፣ ሰባ በመቶ አይፈልግም። የሰጡትም ሃሳብ አሰብ ብቻ ለኢትዮጵያ ተሰጥቶ ሌላው ለጣልያን በሞግዚትነት እንዲሰጥ ነበር።

በዚህ አኳኋን አራቱ መንግሥቶች ስምምነት ስላጡ የፓሪስ የሰላም ውል እንደሚያዘው ጉዳዩ ለዩናይትድ ኔሽን ቀረበ።

በዩናይትድ ኔሽን ጉዳዩ ተመታየቱ በፊት እየዞርኩ ተአራቶቹ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮች ጋር ተገናኝተን ማስረዳት አስፈላጊ መሆኑን ተረዳሁት። በመጀመሪያ ተጀነራል ማርሻል ጋር፣ የአሜሪካን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው፣ በ1948 ፓሪስ ላይ የዩናትድ ኔሽን ጉባዔ ስለነበረ እዚያ ነው ሁሉንም ያነጋገርኩት። እራሱ እንዲያነበው በማሰብ አጭር ሚሞራንደም አሰናድቼ ሄጄ ነበር።

እሥመራንና ምጽዋን ያስከለክሉን ማስተዳደር አይችሉም በማለት መሆኑን ስለገመትኩ፣ ተእሥመራ አምስት ጊዜ የሚበልጥ ሕዝብ ያለበትን አገር አዲስ አበባ ስናስተዳድር እንዴት እሥመራን ማስተዳደር አንችልም? ምጽዋም በገቢው የሚተዳደር መሆኑን ተስታስቲኩ ጋር አስረዳሁት፣ በሚገባው መንገድ። «አሜሪካን የቲኒኒሽ አገሮች ጠባቂ ሆና እኛ መጀመሪያ ቪክትም የሆነው፣ በየጊዜው የወረራ በር የሆነውን ፖርትና አገር፣ የኢትዮጵያ ዋና ታሪኳ የተጀመረበትን አገር /አዱሊስን/ እንዴት ትከለክሉናላችሁ? እኛ መቼም ወገን የሌለን ትንሽ አገር ነን፣ የምንጠይቀው ጆስቲስ ነው። ይህንንም እናንተ አሜሪካኖች፣ እንተ ኮሊኒአሊስቶች የሆናችሁ፣ ተከለከላችሁን ምን እናደርጋለን» በማለት፣ በሚያሳዝን አኳኋንና በሚገባው መንገድ አስረዳሁት። በመጨረሻም «ይህን አጭር ማስታወሻ ራስዎ እንዲያነቡት

እለምናለሁ። የያዘውም ፋክት ብቻ ነው፤ አንድ ነገር ውሸት ሆኖ ቢገኝ ሁሉም ይቅርብን» አልኳቸው። እሳቸውም በትካዜ እኳ.ኒን ሁሉንም ሰምተው ማስታወሻውን ተቀብለው «እነበዋለሁ፤ ተፕሬዚዳንት ቱሩማን ጋርም ተመካክሬ መልሱን እስከ አሥራ አምስት ቀን እሰጥሃለሁ» አሉኝ።

ተአሥራ አምስት ቀን በኋላም አስጠርተው መልስ ሰጡኝ፤ ቀጥሎ ያለውን። «ተፕሬዚዳን ቱሩማን ጋር ተመካክሬ ተአሥመራም ምጽዋንም፤ ተአሰብ ጋር ሌላውንም ተእቆርጻት ሲቀር ለኢትዮጵያ እንዲሰጥ አሜሪካን ይስማማል። ግን አንድ ምክር የምሰጥህ ታንድ ወር በኋላ በአሜሪካን የፕሬዝዳንት ምርጫ አለ። ግምቱ የሪፑብሊካን ፓርቲ ያገኛል ነው። ይህም ሲሆን ፕሬዝዳንቱ ዝቨርንር ዲ.ዊ /ኖኒዮርክ/፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የሚሆነውም ሚስተር ዳላስ ነው። ዳላስም አሁን በኛ ዴሊጌሽን ውስጥ ስላለ እሱን ለኔ የነገርከኝን ሁሉ ብታስረዳው ይጠቅማል» አሉኝ። እኔም በጣም አመስግኜ ተሰናብቼ ሄድኩ።

ዳላስንም በቀጠሮ ተገናኝቼ ለማርሻል እንዳስረዳሁት አደረግሁ። ሚሞራንደምም ሰጠሁት። እሱም በመጨረሻ «ይህን ሁሉ ለኔ የምታስረዳኝ ለምንድነው? እኔ ምንም አይደለሁ» ሲል፣ «ምናልባት በቅርቡ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሳይሆኑ አይቀሩም» አልኩት። በመደሰት ከት ብሎ ሳቀ። በመጨረሻም ተዝቨርንር ዲዊ ጋር ተመካክሬ መልሱን እስከ ስምንት ቀን እሰጥሃለሁ አለኝ። ተስምንት ቀን በኋላ አስጠርቶ ምርጫውን ያገኙን ጊዜ ማርሻል እንዳለው እኛም ኤርትራን እንድታገኝ እንደግፋለን ብሎ አረጋገጠልኝ። /ምርጫውን ግን አላገኙም፤ ትሩማን ነው ያገኘው። ተዳላስ ጋር ባንድ ሆቴል ስለነበርን ተገናኝተን ተወያየን።/

**ተንግሊዞች ጋር እንደዚሁ ተገናኝቼ ተነጋገርኩ።** ኢትዮጵያዊ የሆኑትን ወንድሞቻችንን እንዴት በሞግዚትነት አስተዳድሩ ትሉናላችሁ? ወዳጆቻችን፤ ጃንሆይን የተቀበላችሁ፤ አምስቱን ዓመት ሙሉ ተስፋችን የምንላችሁ በማለት። እነሱም «አሜሪካኖች ናቸው ያስቸገሩት፤ አሥመራም ምጽዋም ለኢትዮጵያ አይሰጥም ስላሉ፤ የሙስኮብና የፈረንሳይን ሙተው ነው፤ እነሱ ሁሉም ሰጣልያን ይመለስ ነው የሚሉት። ስለዚህ አሜሪካኖችን ኩንቪንስ ታደረግህ እኛ ኤርትራ /ተእቆርጻት በቀር/ ለኢትዮጵያ

ቢመለስ እንቃወምም» ሲሉ፣ እኔም ተአሜሪካኖች ጋር ያደረግሁትን ስምምነት ስገልጥላቸው እኛም በዚሁ እንስማማለን አሉ። /የእቅርዳትን ሁለቱም ጠንክረው በዘርም፣ በሃይማኖትም ተናንተ ጋር ግንኙነት ስለሴለው ወደፊት ይታያል በማለት ነው፤ የእንግሊዝ ሃሳብ ግን ተሱዳን እንዲቀሳቀል ነበር።/ እኔም ይሄን ያህል ታስቀበልኂቸው የዩናይትድ ኔሽን ጉዳዩ ሲቀርብ የእቅርዳትን በወዳጅ መንግሥት በኩል፣ ለእነዚህ፣ አብሮ በኢትዮጵያ እንዲላክ አደርጋለሁ ብዬ አቅጄ ነበር።

**የፈረንሳይና የመስኮብ ሁናቴ ልዩ ምክንያት አለው።** መስኮብ በጣልያን አገር በቺጉሎቲ የሚመራ ኃይለኛ የኮሚኒስት ፓርቲ ስላለ፣ መስኮብ ጣልያንን ረድቷል ተብሎ የኮሚኒስት ፓርቲ በኢሌክሽን ምርጫ አግኝቶ መንግሥቱን እንዲይዝ ለማድረግ ነው።

ፈረንሳይ ሁሉም ለኢጣልያን ይመለስ የሚለው ሊቢያ ነጻ መንግሥት የሆነ ጊዜያት ለአልጀርና ቱኒዚ የቅኝ ግዛቱ ስላሲጋ ነው። «ሊቢያና ኤርትራ ምንም አያገናኛቸው። ኤርትራ ለኢትዮጵያ ብትሉ ምን ይጉዳችኂል? ያሉብትም ኢስት አፍሪካና ኖርዝ አፍሪካ ነው» በማለት ተሚኒስተር ቢዶ ጋር ብዙ ብክራክርም፣ «የፕሪንሲፓል ጉዳይ ነው፣ መለያየት አይቻልም» ብለው በዚሁ ከረረ። መስኮብም እንደዚሁ። ሁሉም የራሱን ጥቅም እንጂ በፖለቲካ ጀስቲስ እንደሌለ የታወቀ ነው። ግን ፈረንሳይ ምንም ኢንፍሉየንስ ያን ጊዜ ስለሌላት /የተሸነፈች በመሆኗ/፣ መስኮብም ያለው ወገን ተዎስትና ታራት የማይበልጥ ስለሆነ፣ ተሃምሣ ሁለት መንግሥታት ውስጥ የሚበልጠው ድምጽ ለኛ እንደሚሆን በመገመት ወደ ጉባዔው ለመሄድ መሰናዳት ጀመርኩ። ይህ ግምት ነው። ጉባዔው ሲከፈት ግን የየመንግሥቶቹ ትክክለኛ አቋም ያን ጊዜ ነው የሚታወቀው። ለምሳሌ፣ 21 የአሜሪካ ላቲን አገሮች አሜሪካኖችን ይከተላሉ በማለት፣ እንደዚሁም የኮመንዌልዝ አገሮች እንግሊዝን።

## 6.2 የኤርትራ ጉዳይ በዩናይትድ ኔሽን ጉባዔ

የ1948 እ.ኤ.አ. የዩናይትድ ኔሽን ጉባዔ ፓሪስ ላይ ተደርጎ ሁለተኛው ክፍል ኒዮርክ ላይ ተደረገ። ያራቶቹም መንግሥታት ሪፖርት ቀረበ። ጉባዔው አንዳንድ ንግግር ታደረገ በኋላ የኛን ፖዚሽን በሚገባ አስረዳሁ፤ በሙሉ ጉዳዩ በ1949 በሚደረገው ጉባዔ እንዲታይ ተወሰነ።

በዚህም ጉባዔ ጊዜያት የያንዳንዱን አገር አቋም ለማወቅ ቻልኩ። ተዚህ ቀጥሎ እንዳለው ነበር።

- የላቲን አሜሪካ ግሩፕ /በሙሉ የላቲን አሜሪካን አገሮች እንአርጀንቲን፤ ቺሊ፤ ቬንዝዌላ፤ ሜክሲኮ፤ ወዘተ.../ ሁሉም ካቶሊክ ስለሆኑ፤ የጣልያን ዘሮች ባንዳንዶች ብዙ ስላሉ በጳጳሱ /በሮማ/ ኢንፍሉወንስ ውስጥ ነበሩ። አሜሪካኖችም ጣልያንን ላለማስቀየም በነሱ ላይ ፕሬዠር አላደረጉም ነበር። ስለዚህ የላቲን አሜሪካን ግሩፕ በሙሉ ጣልያንን ይደግፉ ነበር።
- የአረቦች ግሩፕ /ግብጽ፤ ኢራክ፤ ኢራን፤ ሳውዲት አረብ፤ ሊባን፤ አማን/ በሃይማኖት ምክንያት ኤርትራ ተኢትዮጵያ ጋር ተምትቀላቀል ነጻ እንድትሆን ነበር የሚደግፉት።
- የእስያ ግሩፕ /ህንድ፤ ፓኪስታን፤ በርማ፤ ሴሉን/ በእስያ ኮሎኒ ሆነው ስለነበረ በፕሪንስፕል ነጻነት እንጂ ኢትዮጵያ እንድትቀላቀል አይደግፉም ነበር፡- ፓኪስታንም ዋና የስላም ፋናቲዝም ይዞት በጣም ተቃዋሚያችን ሆነ።
- የኮመንዌልዝ ሌሎች አገሮች እንደ አስትራሊያ፤ ኒውዘርላንድ፤ ካናዳ፤ ሳውዝ አፍሪካ /ተካናዳና ተኒውዚላንድ በቀር/ ተቃዋሚያችን ነበሩ።
- በአፍሪካ ተግብጽ በቀር ነጻ የሆን ላይቤሪያ ብቻ ነበረ። ላይቤሪያም ደጋፊያችን ነበር።
- አውሮፓ፡- የአራት መንግሥቶች ከላይ ተነግሯል። ሌሎቹ እንደ ቤልጅክ፤ ሆላንድ፤ ዴንማርክ፤ ሲዊድን፤ ኖርዌይ ያሉት ወይም እንግሊዝን ይከተላሉ ወይም ኒውትራል ነበሩ። እንግሊዝ ግን በነሱም ላይ ሆነ በኮመንዌልዝ አገሮች እንዳችም ፕሬዠር አላደረገ።

በዚህ አኳኋን ተአምሳ ሁለት መንግሥታት ወደ ዘጠና እጁ እኛን አይደግፉም ማለት ነው። የኤርትራና የባህር በር የማግኘታችን ጉዳይ፣ ለኛ ቫይታል የሆነው፣ ዩናይትድ ኔሽን ላይ በድምጽ ብልጫ እንደሚበላሽ ተረዳሁ።

## 6.3 በየአገሩ ያደረኩት ጉብኝትና ተየመንግሥታቱ ያደረግሁት ንግግር

ጉባዔው ተመክፈቱ በፊት ተገቢ በሆኑት አገሮች እየዞርኩ የኢትዮጵያን ጥያቄ ማስረዳት አስፈላጊ መሆኑን ለጃንሆይ ሀሳቡን አቅርቤ አሳቸውም በሙሉ ተስማሙበት። እኔም መጀመሪያ ግብጽን /ሕሱን ኮንቪንስ ታደረግሁ ሌሎቹ አረብ አገሮች ያን ጊዜ እሱን ስለሚከተሉ/ ሁለተኛ አውሮፓን፣ 3ኛም ላቲን አሜሪካ /ሁለት ድምፅ ያላቸውን/ እንደዚሁም የአራቱ መንግሥታት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮች እንደገና በማነጋገር በተከታዮቻቸው ላይ አስፈላጊውን ፕሬዠር እንዲያደርጉ እቅድ አወጣሁ።

በዚህም ፕላን መሠረት ለያንዳንዱ የሚሰጠውን ማስታወሻና ዶኩሜንት፣ እንደፖለቲካቸው አመራር የሚነገራቸውን፣ አስፈላጊ ለሆኑትም ዲኮሬሽን እንዲሁም የጃንሆይን ደብዳቤና ፎቶግራፍ ይዤ ጉዞዬን ጀመርኩ። ተኔ ጋርም አቶ ተስፋዬ ተገኝ፣ ያን ጊዜ ፓሪስ ሚኒስትር የነበሩት፣ አቶ እምሩ ዘለቀ፣ የኔ ጸሐፊ የሆኑት ነበሩ።

መጀመሪያ ግብጽ ከንጉሥ ፋሩክ ጋር ተነጋገርኩ። እንዲሁም ተጃንሆይ የተሰጠውን መልእክትና የሰላምን ኮርዶን ሽልማት ሰጠሁ። ተውጭ ጉዳይ ሚንስትሩም ጋር እንድነጋገር ቀጠሮ ተደርጐ በረጅሙ የኛን ፖዚሽንና የጥያቄያችንን ምክንያት፣ ግብጽ ዓባይን እንደምትጠጣ ሁሉ እኛን መርዳት እንዳለባት፣ እንግሊዞችንም ሌሎቹንም አረብ አገሮች ምክሯን ሰጥቶ እንዲረዱን እንድታደርግ። በመጨረሻም ንጉሡም፣ መንግሥቱም ኢትዮጵያን ለመደገፍ ቃል ገብተው ትእዛዙንም ኒዮርክ ላለው ወኪላቸው ደፍውዚ /በኋላ የውጭ ጉዳይና ጠቅላይ ሚኒስትር የሆነው፣ በናስር ጊዜያት/ እንደሚያስተላልፉ ቃል ገቡልኝ።



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ የግብጹን ፕሬዚዳንት አንዋር ሳዳትን ሲቀበሉ።

## አውሮፓ

ፈረንሳይ አገር መንግሥት ተለውጦ በቤዶ ሥፍራ መስዩ ሹማን የውጭ ጉዳይ ሚንስትር ሆኖ ነበር። እሱም ያስረዳሁትን ሁሉ ተሰማ በኋላ /የኢትዮጵያንና የፈረንሳይ የወዳጅነት ታሪክ ... ሁሉ ዘርዝሬ ነበርና፤ ደግሞም አሜሪካንና እንግሊዝ ሲደግፉን ፈረንሳይ፣ እኛ አገር ባቡር ያለው፣ እኛን አለመደገፉ የሚያስገርም መሆኑን ጭምር/ «የበፊቱን መንግሥት ፖሊሲ አልደግፍም፤ ስለኤርትራ ኢትዮጵያን እንደግፋለን፤ እኔው ራሴ ለጉባኤው ስለምሄድ እዚያው ታየዋህ» አሉ።

## እንግሊዝ

ቤቪን ፖሊሲአቸውን አስመለወጣቸውን አረጋገጡልኝ፡፡ ግን በተከታዮቹ ላይ የሚያስፈልገውን ምክር እንዲሰጥ ጠይቄው፤ «እኛን አይሰሙንም፤ የተቻለኝን አደርጋለሁ» አለኝ፡፡ በኋላም ቤልጅክን፣ የእንግሊዝን ፖሊቲካ ነው የሚደግፍ፣ እንዲሁ አስረዳሁ፡፡

ተዚያም ተለንደን በቀጥታ ወደ ብራዚል /ላቲን አሜሪካን/ ተጓዝን፡፡ አውሮፕላኑ ትንሽ ስለነበረ /ዳኮታ ይመስለኛል/ ለመድረስ 30 ሰዓት ፈጀብን፡፡ ብዙ ችግርም ደርሶብን ከፕሬዚዳንቱ ስንገናኝ የሰላምን ኮርደንና የጃንሆይን መልእክት፣ እንዲሁም የጃንሆይን ፎቶግራፍ ሰጥቼ ጉዳዮችንን አስረዳሁ፡፡ ተውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ጋር እንድንነጋገር ቀጠሮ ተደርጎ ተገናኘን፡፡ እሳቸውም ፈርናንዲዝ የሚባሉ፣ የ70 ዓመት አዛውንት፣ በፊት በሊግ ኦፍ ኔሽን ጊዜ የማውቃቸው ናቸው፡፡ በኋላም ዩናይትድ ኔሽን በየጊዜው እንገናኝ ነበር፡፡ በምን እንደመጣሁ ሲጠይቁኝ በአውሮፕላን ስላቸው ተገርመው፤ «ይህ እግዚአብሔርን ዲፋይ ማድረግ ነው፤ የሚገባ አውሮፕላን ሳይኖር እንዴት ተሎንዶን ጀምሮ እዚህ ድረስ በማይረባ አውሮፕላን ይመጣል? ኒዮርክ እንኳን ስሄድ በመርከብ ነው» አሉኝ፡፡

ለእሳቸውም የምኒልክ ኮርዶን ይገባ ነበርና እሱን መቼ እንደምሰጣቸው ጠየቅሁ፡፡ «ተራት ግብዣ፣ እዚያ ነው የምትሰጠኝ» አሉኝ፡፡ እንደዚህ መንገዱን ካሰናዳሁ በኋላ ንግግሩን ጀመርን፡፡ በሙሉ የጣልያን ደጋፊ መሆናቸውን ተረዳሁ፡፡ «ጣልያን ብዙ ሕዝብ አለው፤ እንደሌሎቹ ብዙ ኮሎኒ የለውም፤ ያላቸው ኤርትራና ሶማሌ ናቸው፤ ጣሊያኖች እንዳስረዱኝ በኤርትራ ብቻ 300,000 ጣልያኖች አሉ፡፡ እነኝህ ሁሉ የት ይሂዱ ማለትህ ነው?» ብለው ኮንቪክሽን መንፈስ ተናገሩ፡፡ እኔም የጣልያን ኢንሳይክሎፒዲያ እንዳላቸው ጠይቄ ስላመጡ፣ ኤርትራንና ሶማሌን የሚመለከተውን ገጽ እንክፈት ብዬ ከፈትን፡፡ እዚያም ላይ እስከ 1934 /እ.ኤ.አ./ በኤርትራ ታንድ ሺህ ጣልያን የበለጠ እንደሌለ እንደዚሁም በሶማሌ ተእራት መቶ የማይበልጥ መሆኑን መጽሐፉ ገልጦ ተገኘ፡፡ እሳቸውም ተገርመው፤ «ታዲያ

300,000ውን ተየት ነው ያመጡት?» አሉ። «እነኝህ ኢትዮጵያን ተወረሩ በኋላ ባምስቱ ዓመት ውስጥ የመጡት ወታደሮችና ሚስቶች፣ ሌላውም ለመኖር የመጡ ጣልያኖች፣ አሁን ወደ አገራቸው ለመመለስ በኤርትራ በየተራ መርከብ የሚጠብቁ የነበሩ ናቸው። አሁን ሁሉም ሄደዋል፤ ተ15ሺህ የሚበልጥ የለም» አልኩ። «እንዲያውም ኤርትራና ሱማሌ ደሃ አገር ስለሆኑ ለገለማ (settlement) አይሆኑም፤ ይህን ዘመን ሙሉ /60-70 ዓመት/ ጣልያኖች ሲገዙ ይሄው ተ400 ወይም 1000 የበለጠ ጣልያን ለማስፈር አልቻሉም። ዋናውም ምክንያት እነኚሁን አገሮች የያዙት ኢትዮጵያን በሚወሩበት ጊዜ መቆናጠሜ ለመያዝ ነው። ለዚሁም ማስረጃ ሞሬስ ራብ /ጣልያን/ የጻፈው መጽሐፍ፡ መቅድም ውስጥ ሞሶሉኒ የጻፈውን መቅድም ማንበብ ነው» አልኳቸው። አላየሁትም ሲሉም፣ ባጭሩ ቀጥሎ ያለውን ነገርኳቸው። «'ኤርትራንና ሱማሌን፣ በረሃ የሆኑትን አገሮች፣ ለምንድነው ጣልያን ይዛ ኪሣራ በየዓመቱ የምትገባው፤ ተባጀቷ ገንዘብ እያወጣች? ምንም ለማያመጡላት። ሌሎች አገሮች ፈረንሳይና እንግሊዝ ኮሎኒ ስላላቸው ለፕሬስቲጅ ነውን?' እያለ ዓለም ይጠይቅ ነበር። አሁን ምክንያቱን ልንገራችሁ። እነኝህ በረሃ የሆኑት አገሮች ላይ ገንዘባችንን እየከሰከስን የተቀመጥነው እነኝህ ሁለት አገሮች በጂኦግራፊም፣ በዘርም የኢትዮጵያ አካልና ኖርሉንጌሽን ስለሆኑ አንድ ቀን ይህን ሪችና ለምለም የሆነውን ኢትዮጵያን ለመያዝ በማሰብ ነበር፤ አሁን ይህ በፋሽስት ረጅም ጊዜ ተፈጸመ» የሚል ነበር። መጽሐፉ የተጻፈው ጣልያኖች ኢትዮጵያን ተያዙ በኋላ ነበር። ይህን ሁሉ ሲያዩ ፈርናዲዝ በጣም ተገረሙ። ተመንግሥቱ ጋር ተመካክሬ መልሱን እስታውቃለሁ ብለው በማግሥቱ ተተኩል ቀን በኋላ ተቃጠርን። በማግሥቱ ወደ ሰላሳ አምባሳደሮች፣ ናሲ አፓስቶሉክም ጭምር፣ ሌሎች ሚኒስትሮች ባሉበት ታላቅ የምሳ ግብዣ አደረጉልኝ። በቶስት ጊዜ ዲስኩር ሲያደርጉ፣ «ብልጅነቴ የአድዋ ዘመቻ ነበር። ተማሪ ቤት ሆኜ ተማሪዎች ወገን ለይተን እንጣላ ነበር። እኔ የምኒልክ ወገን ነበርኩ» ብለው ተናሩ /የምኒልክን ኒሻን ስጥቻቸው ለብሰው ነበር/። ይህም ተኩሉ ቀን በኋላ ለምንነጋገረው ምልክት ሰጠኝ።

በንግግሩም ጊዜያት «ጉዳዩ አሁን ገብቶናል። እኛ ላቲን አሜሪካኖች ተቅኝ ግዛት የወጣን ስለሆን ጀስቲስን ነው የምንደግፈው፤ አሁን እንደተረዳነው ጀስቲስ ለኢትዮጵያ ይገባታል። ስለዚህ ነው ኢትዮጵያን የምንደግፈው» ብለው ቃል ሰጡኝ። እኔም አመስግኜ ለወዳጅ አገሮች ሁሉ ይህንኑ እንዲያስረዱ ለምኜ ተለያየን።

ለመጎብኘት የታቀደው ዋናዎችን ቁልፍ የሆኑትን አገሮች ተጠንተው አምስቱን ነበር፦ ብራዚል፤ አርጀንቲን፤ ቺሊ፤ ቬንዝዌላ፤ ሚክሲኮ፤ ሌሎቹ እነሱን ይከተሉ ነበር።

አርጀንቲን ያን ጊዜ የነፐሮን [Juan Domingo Perón] ጣልያን ሬጅም ነበር። በመንግሥቱ የሚበልጠው ጣልያኖች ስለነበሩ፣ ተቀብሉ ለማነጋገርም ስላልፈቀዱ አንድ ቀን አድረን ወደ ቺሊ ሄድን።

ቺሊ ደህና ተቀበሉን። በደረስን ማግሥት መንግሥቱ ተገልብጦ ሌላው እስቲቋቋም ቆየን። ተዚያም በኋላ ለፕሬዚዳንቱና ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ተገቢውን ሽልማትና መልክት ተሰጠሁ በኋላ ብራዚል በተነጋገርኩበት አኳኋን አስረዳሁ። እነሱም ለመደገፍ ቃል ሰጡ።

ከፔሩ፤ ቬንዝዌላና ሚክሲኮ ብራዚል በተደረገው አኳኋን ንግግሩ ተደረገ፤ አቀባበላቸውም ደህና ነበር። ለመደገፍ ቃላቸውን ሰጡ። ሁሉም ያሉኝ፤ «የኢትዮጵያ ሰው መጀመሪያ ጊዜ ነው አገራችን የመጣው። አሁን ገብቶናል፤ ኤምባሲ እየከፈታችሁ ሁልጊዜ ኮንታክት ማድረግ ጠቃሚ ነው።» በጉብኝት ጊዜያት የተወሰደው ፎተግራፎች፤ የጃንሆይ ደብዳቤ ኮፒ፣ ሌላም ይህን መሰል አርካይቭ ውስጥ ይገኛል። ተዚያም በመለስ ዋሽንግተን ደርሼ ተአሜሪካን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ዤ. ሙስተር አቼሰን ጋር በረጅሙ ተነጋገርን — የላቲን አሜሪካን ጉዞና የተሰጠውን ቃል፤ አሜሪካኖችም ርዳታቸውን እንዲቀጥሉ። በጣም ድካም ላይ ስለነበርኩ ዶክተርስ ሆስፒታል ገባሁ።



ጠቅላይ ሚኒስትር እክሊሉ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ የልደት በዓላቸውን ሲያከብሩ አብረው የተነሱት ፎቶግራፍ፡፡

ታምስት ቀን በኋላ ወደ እንግሊዝ አገር ሄጀ ለሚስተር ቤቪን ሁሉንም አስረዳሁ፡፡ ተኔ ጋር የነበሩት አቶ ተስፋዬ ተገኝ በጣም ድካም ላይ ስለነበሩ ተሁለት ወር በኋላ ሞቱ፡፡ አዲስ አበባ እንደገባሁ ለጃንሆይ ራፖሬን አቅርቤ በቶሎ በብራዚል፣ በቬንዝዌላና በሜክሲኮ ኤምባሲ እንዲከፈት ሃሳብ አቅርቤ በዚሁ ተፈጸመ፡፡

## 6.4 በዩናይትድ ኔሽን የተደረገው ዲቤት /1948—1950/

እዚህ ባጭሩ ነው የምዘረዝረው፤ ሁሉንም ለማየት ዶኩሜንቱን፣ ፕሮሲቬርባሉን፣ በዩናይትድ ኔሽን የተደረገውን ዲስኩሩን ሁሉ /ታምስት ሙቶ ገጽ የማያንስ/፣ ሚሞራንደሙን ማየት ያስፈልጋል፤ ሁሉም አለ።

ሀ/ በ1948 የተደረገው ላይ ተነግሯል /ዶኩሜንቱን ማየት/።
የኤርትራ ጉዳይ በ1949 ለሚደረገው ጉባኤ ፖስትፖንድ ሆነ።

ለ/ በ1949 እላይ እንደተዘረዘረው አስፈላጊ የሆኑትን አገሮች ሁሉ እየዞርኩ የኢትዮጵያን ጥያቄ ሁሉ አስረድቼ ነበር፤ ጉባዔው ሥራውን ተመጀመሩ በፊት።

- *የቬቨንና የስፎርጎ ፕላን የተባለው*

የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርና የጣልያን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በመንግሥታቸውና በወገኖቻቸው ስም ስለጣልያን ቅኝ አገሮች ውሳኔ አንድ ፕላን አቀረቡ፤ ባጭሩ ቀጥሎ እንዳለው ነበር።

ሀ/ ሊቢያን እንግሊዝ፣ ፈረንሳይ፣ ጣልያን፣ ተከፋፍለው በሞግዚትነት ለአስር ዓመት እንዲያስተዳድሩ፤

ለ/ ኤርትራ ተአቆርዳት በስተቀር ለኢትዮጵያ እንዲሰጥ፤

ሐ/ ሱማሌን ጣልያን በሞግዚትነት ላስር ዓመት እንዲያስተዳድር።

**በክርክሩ ጊዜያት** /በፖለቲካ ኮሚሲዮን/ አቆርዳትም ተሌላው ተኤርትራ ክፍል ጋር ለኢትዮጵያ እንዲሰጥ በፈረንሳይ በኩል /ያን ጊዜ ኩቭ ደሞርቪል ነበረ/ ሃሳብ ስለአቀረብኩ አሜሪካኑም፣ እንግሊዞችም፣ ተከታዮቻቸውም ተቃወሙት። በድምጽ ወደቀ፤ ሌላው ፕላን በሙሉ የድምጽ **ብልጫ አገኘ**፤ ተዚህም በኋላ ሬዞሊሽን ለዋናው ጉባዔ ቀረበ፤ አንቀጽ በአንቀጽ ድምጽ እንዲሰጥ ስለተጠየቀ በዚሁ አኳኋን ድምጽ መስጠት ተጀመረ። ኤርትራ ለኛ እንዲመለስ ታስፈላጊው ድምጽ በላይ (2/3) ተገኘ፤ ለፈረንሳይና እንግሊዝ አሊቢያ ክፍል 2/3 ድምጽ አገኘ፤ የጣልያን ግን በሱማሌ ሲያገኝ በሊቢያ አላገኘም። ተዚህ በኋላ

በሬዞሊሽኑ በጠቅላላው ቮት ሲደረግ ፈረንሳይና የላቲን መንግሥት አገሮች /በፈረንሳይ ተመርተው/፣ «ጣልያን ታላገኙት ማገንም አያገኙ፤ ሁሉም የተያያዘ ነው፤ ግን በኢትዮጵያ ላይ ቮት አላደረግንም፤ እሷ ከሚያስፈልገው በላይ ድምጽ አግኝታለች፤ ግን ሬዞሊሽኑ የተያያዘና አንድ አካል ነው። እናገዞናለን» ብለው፣ ዲሞክራሲዎን አደረጉ። ድምጽ ተተሰጠም በኋላ ሬዞሊሽኑ ማጆሪቲ እንጂ ተሦስቱ ሁሉቱን እጅ አላገኘም። በዚህ ምክንያት ፕላኑ ወደቀ፤ የኤርትራም ጉዳይ ሳያልቅ ቆየ።

በኋላም ዲቤት ቀጠለ። በኮሚስዮን ውስጥ ሁለተኛ የኤርትራ ሕዝብ ወኪሎች የተባሉት ተጠርተው ነበር፤ ከልዩ ልዩ ፓርቲ ነበሩ። የነጻነት ፓርቲ፣ በዩናይትድ ኔሽን ሞግዚትነት እንተዳደር የሚሉ፣ በእንግሊዝ ... መሪዎቻቸውም እነ ወልደአብ፣ ኢብራሂም፣ ሱልጣን። እነሱም ሲደመሩ በመቶ ስልሳ የኤርትራን ሕዝብ ወክለናል እያሉ ዲሞክራሲዎን ሲያደርጉ ጉባዔው ኢምፕሬስ መሆኑ አልቀረም፤ እኛን የሚደግፍ አንድ ፓርቲ ብቻ ነበር። ይኸውም የዩኒየን ፓርቲ በዋናው ጸሐፊ በተድላ ባህሩ ይመራ ነበር /በአራቱ ኮሚስዮን ሪፖርት ውስጥ ይህ ፓርቲ ከ30-40 በመቶ ብቻ ነው የኤርትራን ሕዝብ የሚወክለው ተብሎ ነበር የቀረበው/።

እኛን የሚቃወሙት ፓርቲዎች ተጣልያን ጋር ተስልፈው፣ ጉን ለጉን ተቀምጠው፣ እኛን ሲቃወሙ ማየቱ በጣም ያሳዝነኝ ነበር። በየተራ ሁሉም ዲስኩራቸውን አደረጉ። ተዚያም በኋላ ደንቡ እንደሚሰጠኝ ልዩ ልዩ ጥያቄ እያቀረብኩ በጉባዔው ላይ የፈጠሩትን ኢምፕሬሺን በከፊል አፈረስኩት። ለምሳሌ፣ ወልደአብ የኢንቴሌክቹአል ፓርቲ /Intellectual Party/ መሪ ነኝ ብሎ ነው ዲስኩሩን ያደረገው፤ አምስት ስድስት መልክተኞች ይሆኑ ነበር። ለጉባዔው ይህ ኢንተለጀንሲያ /የተማሩት ክፍል/ ሁሉ ኢትዮጵያን የሚቃወሙ መስሎ ነው የሚታየው፤ ሁለት ጥያቄ አቀረብኩለት።

«ስንት ሰው አለበት፣ ያንተ ፓርቲ?»

መልስ፦ «ተመቶ እስከ ሁለት መቶ አምሳ።»

«ተንኘህ መካከል ተነስማቸው ስንት ለማትሪኩሌሽን ወይም ሌላ ዲግሪ ያላቸውን ዝርዝር ለመስጠት ትችላለህን?» መልስ፡- «ምንም የለ። እንዴት ኢትዮጵያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ይህን ይጠይቀኛል? በቅኝ አገዛዝ በጣልያን ተይዘን መቼ እስተማሩን?!» /መልክተኞች ሁሉ ሳቁ/።

እኔም፣ «ይህን መቼ አጣሁት፣ አንተ የቀረብከው የኢንቴሌክቹአል ፓርቲ ብለህ ስለሆን፣ እውነት የተማሩት ፓርቲ እንዳልሆንክ ጉባኤው እንዲያውቀው ነው። ጣልያኖች አንድም ኤርትራዊ ያስተማሩት የለም፣ ያስተማረቻቸው ኢትዮጵያ ናት። ለምሳሌ፣ እኔ ጎን ያሉት ኤርትራዎች እነ ብላታ ዳዊት፣ አቶ ገብረመስቀል እና ሌሎቹም የሌሉ በብዙ መቶ የሚቆጠሩ እያመሰጡ እየመጡ እኛ ያስተማርናቸው ናቸው» አልኩ።

ኢብራሂም ሱልጣን፣ የሙዝሊም ሊግ አለቃ፣ ዲስኩሩን ሲያደርግ፣

ሀ/ ኤርትራ መቼም ቢሆን ተኢትዮጵያ ጋር ሆና አታውቅም፣
ለ/ በየአውራጃው እየዘረዘረ 300,000፣ 500,000፣ 700,000 ... ህዝብ የኛ ፓርቲ ነው።

ጥያቄዬን ቀጠልኩ።

ኤርትራ ተኢትዮጵያ ጋር አብራ ሆናም አታውቅ ብለሀል። እንዲህ ተሆን በሁለቱ አገር መካከል ጠረፍ በየት ነበር የሚያልፈው፣ ጣልያን ተመምጣቱ በፊት?

መልስ፡- አላውቅም /ሳቅ/።

ከየአውራጃው ያለህን ደጋፊ የህዝብ ቁጥር ሰጥተሃል። ድምሩ ስንት ነው? ተደምሮ 3 ሚሊዮን ሆነ። «የኤርትራ ሕዝብ ቁጥር ስንት ነው?» ብዬ ጠየቅሁ።

መልስ፡- «አላውቅም። እንግሊዞችን ጠይቃ!» እኔም ታንድ ሚሊዮን አይበልጥም አልሁ፣ ሁሉም ሳቀ።

በክርክሩ ጊዜ መስኮብ አንድ ሪዞሊሽን አቀረበ። እሱም አሰብ ብቻ ለኢትዮጵያ ተሰጥቶ ሌላው ነጻ ይሁን የሚል። ብዙ መንግሥቶች

በነጻነት ላይ አጌንስት ኾት ማድረግ እንችልም አሉ፤ አረቦችም ጭምር፡፡ በጣም ተቸገርኩ፡፡ ይህንን በተቀበልኩ ጊዜያት ኤርትራን መቼም አናገኝ፡፡ የተቃወምኩ ጊዜያትም አሰብንም፤ ሁሉንም ልናጣ እንችላለን፡፡

ወዲያውኑ ጠንካራ የሆነ ዲስኩር አደረግሁ፡፡ «የመስኮብ ሬፐብሊሽን የፒስ ኮንፍረንስን እንቀጽ የሚቃወም ነው /ሰላምን፤ ጸጥታን መሠረት በማድረግ ጥቅም ያላቸውን መንግሥቶች ሃሳብ ኮንሲደሬሽን ተወሰደ/፡፡ «ይህ አገር ለኢትዮጵያ መውረሪያ ቤዝ እንደነበረ መስኮብ ያውቃል፡፡ አሁንም ኤርትራ ነጻ መሆን አትችልም፤ የሌላ መንግሥት መግሪያ ሆና እኛን ለማጥቃት እንዲሆን ታልሆነ በቀር፡፡ ስለዚህ ይህን ሐሳብ የሚደግፍ የሰላም ጠላት፤ የኢትዮጵያም ጠላት ነው ብለን ነው የምንቆጥረው፡፡ ድምጽ ሲሰጥም፤ ስም እየተጠራ ይደረግልኝ» ብየ ጠየቅሁ፡፡ የመስኮብም ተወካይ፤ «ሕዝቡ ተኢትዮጵያ ጋር ነው ብለህል፡፡ እንዲህ ተሆነ፤ ነጻ ተሆነ በኋላ ራሱ ይቀላቀል የለም ወይ! ምን አስፈራህ?» አለኝ፡፡ እኔም «ኢስቶኒያን፤ ሉቱኒያን የያገጮቸው ሕዝብ ከመስኮብ ጋር መቀላቀል ይፈልጋል ብለህ ነው? ለነሱ የፈቀድክላቸውን ለምን ለኤርትራ ሕዝብ ትነፍጋለህ? እስቲ እነሱን አሁን ነጻነታቸውን ስጣቸውና በኋላ ተመስኮብ ጋር ይቀላቀሉ? አንድን ልጅ በእግርህ ሂድ ታልከው በኋላ ራስህን ግደል ብትለው እሽ አይልም» አልኩት /አሜሪካኖችና እንግሊዞች ሊሉቹም የመስኮብ ተቃዋሚዎች ከት ብለው ሳቁ/፡፡ የመስኮብም መልክተኛ ተቆጥቶ ወደ ውጭ ወጣ፡፡

በዚህም ጊዜ የግብጹን መልክተኛ ፋውዚን እንዲሁም የየመንን እውጭ እየወሰድኩ አነጋገርኳቸው፡፡ ፋውዚንን «ለነጻነት ኾት አደርጋለሁ ብለህ የተናገርከው ተመንግሥትህ ተፈቅዶልህ ነውን? እኔ ተዚያ ነው የመጣሁት፡፡ ንጉሡም፤ መንግሥቱም እኛን ለመደገፍ ቃል ሰጥተውኛል፤ አሁን ደውለህ ጠይቅ፡፡ እለዚያ አንተ አላፊ ነህ» ስለው አበደ፡፡ የየመንን «አዲስ አበባ ወደ 20,000 የሚሆኑ ያንተ ዜጎች አሉ፤ መስኮብን ደግፊህ ድምጽ የሰጠህ እንደሆነ አሁኑኑ ቴሌግራም ልኬ ዜጎችህን አስወጣቸዋለሁ» አልኩት፡፡ ሌሎችንም በየመልኩ አነጋገርኩ፡፡

በኋላም ዲቤት ተከፍቶ ክርክሩ ቀጠለ፤ ሌላ አንድ ሬዞሊሽን ቀረበ፡፡ ይኸውም፤ «እስታሁን ድረስ ዩናይትድ ኔሽን ኮሚስዮን ልኮ

በኤርትራ የሕዝቡን ሃሳብ አልጠየቀም /ሕስታሁን የሄዱት ያራቱ መንግሥታት ብቻ ናቸው/። አሁንም ያምስት መንግሥት መልክተኞች በዩናይትድ ኔሽን ስም ሄደው የህዝቡን ሃሳብ ይጠይቁ» የሚል ነበር። ግብጽ ይህንን ምክንያት አድርጎ መስከብን ሃሳቡን ዊዝድሮው እንዲአደርግ ጠየቀው። እሱም እምቢ አለ። የግብጹ ተወካይ እንግዲያውስ በሃሳቡ ላይ ተቃውሜ ነው ድምጽ የምሰጠው አለ፤ ሌሎች አረቦች ይህንኑ ተከትለው አስታወቁ። ሌሎች መንግሥታቶችም ፕራይወሪቲ ለኮሚሽዮኑ መላክ ሃሳብ ይሰጠው፤ ያንተ ይቆይ ቢሉት መስኮብ አልቀበልም አለ። በኋላም ድምጽ ተሰጠ። መስከብን የደገፈ 3 ድምጽ ብቻ ስለሆነ ሃሳቡ ወደቀ።

## 6.5 ወደ ኤርትራ የሚሄደው የዩናይትድ ኔሽን ኮሚስዮን አመራረጥና አባሎች

ለኮሚስዮኑ አባል እንዲሆኑ የተመረጡት አገሮች /ይህም በታላላቅ መንግሥታቶችና በወገኖቻቸው ነው/ ሳውዝ አፍሪካ፣ ፓኪስታን፣ ጓቲማላ፣ በርማና ኖርዌይ ነበሩ። ይህም ሃሳብ በሬዞሊሽን ጉባዔው ፊት በቀረበ ጊዜ በብርቱ ተከራከርኩ። «ሳውዝ አፍሪካና ፓኪስታን በኢትዮጵያ ላይ በዲስኩራቸው ፖዚሽን የወሰዱ ናቸው። የኢትዮጵያ ጠላትነታቸውን በግልጽ ያስታወቁ ናቸው። ጓቲማላም እንዲሁ የጣልያን ጠበቃ መሆኑን አሳይቷል። ተሁለቱ፣ በርማና ኖርዌይ፣ ኒውትራል ተሆኑት በቀር ሦስቱ አሁኑኑ ፕራየር ዲስሽን ያደረጉ ናቸው። የዚህ የዚህ ለምን ጣልያንን አታደርጉትም?» አልኩት። እነሱም ተቃወሙ። አንድ ጊዜ ታላላቆች መንግሥታቶች ተስማምተውባቸዋልና ምንም ማድረግ አልተቻለም። በመጨረሻም በድምጽ ብልጫ እነሱ እንዲሆኑ ተወሰነ።

ቢሆንም ይህንን ሁኔታ ለማሻሻል ታምስቱ መንግሥቶች ጋር ይልቁንም ተሳውዝ አፍሪካ፣ ጓቲማላ፣ ፓኪስታንና በርማ ጋር ንግግር ጀመርኩ። ለያንዳንዱ መንግሥት በሚገባው ሃሳብና በሚቀበለው መንገድ በረጅሙ የኛን ሁናቴ አስረዳ ነበር። ተሳውዝ አፍሪካ ጋር ያደረግሁት ኢንተረስቲንግ ነበር፤ ዝርዝሩ ብዙ ነው። ለፓኪስታን፣

«አንተ እንደምትለው በኢትዮጵያ እስላሞችን እንደአብድ ውሻ እንፈጃቸውም፣ ሄደህ እንድታይ እለምንሃለሁ። ንግዱና ኢኮኖሚው ሁሉ በነሱ መያዙን ታያለህ። በታሪክም መሐመድ ስለኢትዮጵያ ያለውን አስታውስ» አልኩት። እንደዚሁም የንቲማላንና የበርማን አስረዳኋቸው። በርማ አሁን ነጻ የሆነ አገር ስለሆነ ያለ ነጻነት ሌላ ሃሳብ የለውም ነበር። ለኤርትራ ነጻነቷ ተኢትዮጵያ መቀላቀል ነው በማለት፣ በልዩ ልዩ ዘዴ ግብዣ ጭምር፣ ወደ ኤርትራ ተመሄዳቸው በፊት የተቻለውን ያህል አለስልሻቸው ነበር።

## 6.5.1 ኮሚሲዮኑ ጉብኝት በየአገሩ /ኤርትራ፣ ኢትዮጵያ፣ ሱማሌና ግብጽ

ኤርትራን ጎብኝተው ወደ አዲስ አበባ ሲመጡ ስብሰባ በራስ ሆቴል ተደርጐ ነበር። ስልሳ ገጽ የሚሆን የኤርትራን ታሪክ፣ የኢትዮጵያ አካል መሆኗንና እንደምን ጣልያን እንደያዛት፣ ብዙ ጊዜ ኢትዮጵያን መውረሪያ እንደሆነች፣ የሕዝቡን ሃሳብ እውነተኛውን /በእንግሊዝ አድሚኒስትሬሽን ሆኖ እውነተኛ ሃሳቡን ለመስጠት ስላልቻለ/ የዘረዘረ ንግግር አደረግሁ። በመጨረሻም ልዩ ልዩ ጥያቄ አቀረቡልኝ፣ በሚገባ መለስኩ። ዲስኩሩንም፣ ጥያቄውን ሁሉ ከፕሮሲቬርባሉን ማየት ይቻላል። /በዚያን ጊዜም በድካም ብዛት በየጊዜው እታመም ነበር፣ እሆቴሉም ሃኪም ይጠባበቅ ነበር።/ ኮሚሲዮኑም የእስላሞችን ሁኔታ አዲስ አበባ ብቻ ሳይሆን በሌላም ክፍል ሄዶ እንዲያይ አድርገን ጎንደር፣ ሐረር ሄዱ። ብዙ ግብዣም፣ እስላሞች የነበሩበት፣ ተደርጎላቸው ነበር። ፓኪስታኑ በጣም ተደንቀ፣ «የሚያወሩልን ሁሉ ውሸት ነው» አለኝ።

ኮሚሲዮኑ ሱማሌንና ግብጽን ጎብኝቶ /ግብጽን የጎበኘው ምጽዋን ጠይቃ ስለነበረ ይሆናል/ ወደ ዩናይትድ ኔሽን ተመልሶ ራፖር አሰናዱ።

ራፖሩ ታትሞ ለዩናይትድ ኔሽን ቀረበ። ፍሬ ነገሩም ቀጥሎ እንዳለው ነው /ራፖሩን ማየት/።

ሀ/ ሳውዝ አፍሪካና በርማ ኤርትራ ተኢትዮጵያ ጋር በፌዴሬሽን እንድትቀላቀል፣

ለ/ ፓኪስታንና ጓቲማላ ኤርትራ ነጻ እንድትሆን፤
ሐ/ ኖርዌይ፤ ኤርትራ ያለ ኮንዲሽን ተኢትዮጵያ ጋር እንድትቀላቀል።

በዚህ አካኋኋን ታንድ አገር በቀር (ኖርዌይ) የኛን ጥያቄ ሙሉ በሙሉ የሚደግፍ አልነበረም። ሁለቱ ፌዴሬሽን (እውነተኛውን)፤ ሁለቱ ነጻነት እንደመቀላቀልን።

የአሜሪካንን፤ የእንግሊዝን ሃሳብ በብዙ መንገድ እየጠየቅን ተነሱም ጋር እየተመላለስኩ ተነጋገርን። እነሱም ፌዴሬሽን እንዲሆን የሚደግፉ መሆኑን አስረዱ። ይኸውም ኢትዮጵያን ለመደገፍ መሆኑንም አሳወቁ። ተኮሚሲዮኑ ራፖር በኋላ እንዲሁ የመቀላቀልን ሃሳብ ከጉባዔው የሚበልጡት መንግሥቶች እንደሚቃወሙት አስረዱ /አረቦች፤ ላቲን አሜሪካኖች፤ እዚያም ኮመንወልዝ/።

ይህን ጉዳይና ሌላም ለማጥናት ትንሹ ጉባዔ የተባለ የመንግስቶች ሁሉ ወኪሎች ያሉበት ሲሠራ ቆይቶ፤ ለ1950 ጉባዔ ሃሳብ እንዲያቀርብ በ1949 ተወስኖ ስለነበረ ኒዮርክ ሄጄ ስባት ወር ስከራከር ቆየሁ።

ተመሄዴም በፊት ማድረግ የሚገባኝን ተጃንሆይና ተሚኒስትሮቹም ጋር ምክክር ተደርጎ ኢንስትራክሽን ተቀብዬ ነበር። ተሄድኩም በኋላ ለሚደረገው ሁሉ ቴሌግራም በየጊዜው አዲስ አበባ እየላክሁ ትእዛዝና ኢንስትራክሽን እቀበል ነበር። ይህ ሁሉ ቴሌግራም አርካይቭ ይገኛል። እኔም የብዙው ኮፒ አለኝ።

ወደ ኒዮርክም ስሔድ በፓሪስ፤ ሎንዶን፤ ዋሽንግተን አልፌ ተመንግሥቶቹ ባለሥልጣኖች ጋር በሰፊው ተነጋገርኩ። ሎንዶን አምባሳደሩ አቶ አበበ ረታ ነበር። በንግግሩም ጊዜ ተገኝቷል። ባጭሩ ያስረዳሁት፤ «ፌዴሬሽን እንቀበልም፤ አንድነት እንጂ። ያልሆን እንደሁ፤ እውነተኛ ፌዴሬሽን /እንደ አሜሪካን አይነት ሁለት መንግሥት፤ ሁለት ፓርላማ፤ ሁለት ባንዲራ፤ ሁለት ካፒታል፤ ደግሞ ሦስተኛ ፌዴራል መንግሥት፤ ፌዴራል ፓርላማ፤ ፌዴራል ባንዲራ ልንቀበል አንችልም። ባንድ በኩል ፌዴራል ካፒታል፤ ኤርትራ አንድ ጠቅላይ ግዛት፤ በሌላ በኩል ኢትዮጵያ አሥራ ሁለት ጠቅላይ ግዛት

ያላት፣ እንዴት እኩል ተቆጥረው? ለማድረግም አይቻልም። ሕገ-መንግሥቱም የኤርትራ፣ የኢትዮጵያ፣ የፌዴራል፣ ሦስት ሕገ-መንግሥት አንቀበልም። ለኢትዮጵያም፣ ለኤርትራም አሁን ያለው የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ነው የሚረጋው፣ ቢበዛ ቢበዛ ለኤርትራ የምንቀበለው እኩል አድሚኒስትሬሽን ነው። ቢበዛ፣ እንደ ስኮትላንድ ዓይነት። ወይም ሎሬን፣ የፈረንሳይ ክፍል የነበረው፣ በጀርመን ብዙ ጊዜ ተይዞ ተታላቁ ጦርነት /1914—1918/ በኋላ ወደ ፈረንሳይ ሲመለስ በዚህ አኳኋን ነው» በማለት ነበር ያስረዳሁት።



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ከተባበሩት መንግሥታት ዋና ጸሐፊ ኡ ታንት ጋር ሲወያዩ።

ትንሹ ጉባኤ /Little Assembly/ ስባት ወር በክርክር ኒውዮርክ ቆየሁ። የክርክሩ ሁኔቱ፣ በየጊዜው የላኩትና የተቀበልኩት የትእዛዝ ቴሌግራም አለ። ወደኒዮርክ ተመሄዴ በፊት ፓሪስ ሃኪሞች አይተውኝ፣ «ታመሃልና ሆስፒታል ገብተህ ኦፕሬሽን ማድረግ አለብህ» ብለውኝ ነበር። እኔም «ያገር ጉዳይ ስላለ አልችልም» አልኳቸው። እነሱም «አውሮፕላን ላይም አደጋ ሊደርስብህ ይችላል» ብለውኝ ነበር። ዝም ብዬ ሄድኩ። ጉባዔውንና የኤርትራን ጉዳይ ጨርሼ ስመለስ የፓሪስ ሃኪሞች ያሳሰቡኝን ኦፕሬሽኑን አደረገሁ።

በዚህ በጉባዔ ጊዜ አንድ አክት ፌዴራሉን ወይም ዩናይትድ ኔሽን የሚያሳልፈውን ሪዞሊሽን የሚያሰናዳ፣ ስለኤርትራ፣ አንድ ኮሚቴ ተቋቁሞ ነበር፤ እንብራዚል ያሉበት። ብዙ ክርክርም ነበር። ጣልያኖችና ወገኖቻቸው የጣልያንን ጥያቄ እየደገፉ፣ አሜሪካኖችና እንግሊዞች ደግሞ የኛን ጠንካራ አቋም ስላዩ እኛ ለመቀበል የምንችለውን ለማድረግ ሠርተው ነበር። በዚህ ጊዜ ተሁሉም መንግሥታት ወኪሎች ጋር በረጅሙ መነጋገሬን አሳቋረጥኩም፤ ከሕንዶች፣ ፓኪስታንና ላቲን አሜሪካን። በመጨረሻም አንድ የሪዞሊሽን ሃሳብ፤ ስሙ ፌዴሬሽን ይሁን እንጂ ለኤርትራ ሎካል ኦቶኖሚ የሚሰጥ፣ ሌላውን ሁሉ /ፖርት፣ ባቡር/ በኢትዮጵያ መንግሥት ሥልጣን ሥር የሚያደርግ ቀረበ። የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ለኤርትራም እንዲሆን የሚል አሠናድተው ለ1950 ጉባዔ ለማቅረብ አቀዱ።

## 6.6 የ1950 ጉባዔና የኤርትራ ጉዳይ ፍጻሜ ማግኘት

ጉባዔው ላይ የተደረገው ዲቤት ብዙ ዝርዝር ስላለው ፕሮሲቬርባሉን፣ ያደረኩትን ዲስኩርና ኢንተርቬንሽን ማየት አስፈላጊ ነው። እዚህ የማስታውሰውን ያህል ባጭሩ እጠቃልላለሁ።

ጉባዔው እንደተከፈተ ጣልያኖች ታክቲካቸውን ለወጡ። ጥያቄያቸው የሚፈጸም መሆኑን ሲያውቁት ለጣልያን ኮሎኒ ሁሉ ነጻነት ይሰጥ ብለው ሃሳብ አቀረቡ፤ የነጻነት ሻምፒዎን ሆኑ።

የኤርትራን ሕዝብ ወክለናል እያሉ እየመጡ ለጉባዔው ሃሳባቸውን እንዲሰጡ የተፈቀደላቸው ፓርቲዎች አላማቸው የተለያየ ነበር — ጣልያን ያስተዳድረን፣ እንግሊዝ ያስተዳድረን፣ ዮናይትድ ኔሽን ያስተዳድረን፣ ነጻነት የሚሉ ሆኖ ነበር። ኒዮርክ ሲደርሱ ምክር አላማቸውን አንድ አድርገው፣ ሁሉም ነጻነትን ነው የምንፈልገው ብለው አስታውቀው፣ ብሎክ ኢንዲፔንዳንስ የሚል አንድ ፓርቲ መሆናቸውን አስታወቁ። እንደዚህም ሲሆን በአራቶች መንግሥታት ሪፖርት መሠረት ኢትዮጵያን የሚደግፈው ቢበዛ በመቶ አርባ ብቻ ነው ስለተባለ፣ የዩናይትድ ኮሚሽንም ተሞላ ጉደል ይህንኑ ሃሳብ ስለሚደግፍ፣ ተኤርትራ ሕዝብ በመቶ ስልሣው ነጻነት ስለጠየቀ ለኛ አደገኛ ሆኖ ተገኝቶ ነበር።

ለጣልያን ማስታወቂያ፣ «ለኤርትራ ነጻነቷ ተኢትዮጵያ መቀሳቀል ብቻ ነው» ብዬ አስረዳሁ። ኒዮርክ ሲደርሱ አንድ ግንባር አቋቁመው፣ በመቶ 60 የሆነው ነጻነቷን ነው የምንጠይቀው ሳሉት ወኪሎች ዲስኩራቸውን ታደረጉ በኋላ ልዩ ልዩ ጥያቄ አደረግሁላቸው፤ አንዱም ይህ ነበር። «ተኤርትራ ስትነሱ ተወከላችሁ ሕዝብ የተቀበላችሁት ማንዴትና ኢንስትራክሽን ልዩ ልዩ ነበር /ጣልያን፣ እንግሊዝን፣ ዩናይትድ ኔሽንን እንዲያስተዳድራችሁ ለመጠየቅ/። እዚህ ስትደርሱ የወከላችሁን ሕዝብ ሳትጠይቁ እንዴት በራሳችሁ የፈጠራችሁትን ሃሳብ የወከለን ሕዝብ ሃሳብ ነው ለማለት ትችላላችሁ? ይህን ሃሳብ የጸነሳችሁት እዚህ ስትመጡ፣ ሁላችሁም ሮማ ቆይታችሁ ስለነበረ፣ ተጣልያን ጋር በመመካከር አይደለምን?» በዚህ ጊዜ ጣልያኖች የድንጋጤ መልክ ይታይባቸው ነበር። ወኪሎቹም ተቸግረው፣ ሕዝቡን በቴሌግራም ጠይቀናል አሉ። ቴሌግራሙን አሳዩ አልኳቸው፤ አለመኖሩ ተረጋገጠ። በዚህ አኳኋን ጉባዔው ይህ ሁሉ የጣልያን ፋብሪካሲዎን መሆኑን ተረዳው።

በቀረበው ሪዞሊሽን ላይ ክርክሩ ቀጥሎ ሪዞሊሽኑ፣ ፌዴሬል አክቱን የያዘ፣ በብዙ ድምጽ አለፈ /ታህሣሥ 1950 ዶክሜንቱን ማየት። ይህም ሪዞሊሽን ቀጥሎ ያሉትን ዋና ዋና ጉዳዮች ይዘረዝራል።

ሀ/ መቅድም፦ የሕዝቡን ሃሳብ፤ ሰላምንና ጸጥታን፤ የኤርትራን ጂኦግራፊያዊ አቀማመጥና ኢኮኖሚዋን፤ ኢትዮጵያ የባሕር በር እንዲኖራት አስፈላጊ መሆኑን በመረዳት፤ ይህን ሁሉ መሠረት በማድረግ ቀጥሎ ያለውን ሪዞሊሽን አሳልፈናል።

ለ/ ኤርትራ፦ አንድ ዩኒት ሆና ተኢትዮጵያ ጋር በፌዴራል እንድትቀላቀል። የሊባኖስ መልክተኛ ዩኒት መባሉ ቀርቶ ስቴት ይባል ብሎ ሃሳብ ሲያቀርብ በብርቱ ተቃውሜ ሃሳቡ ፈረሰ።

ሐ/ የኢትዮጵያ መንግሥት ስልጣንን ይዘረዝራል። ፖርት፤ ባቡር፤ መከላከያ፤ የውጭ ጉዳይ፤ መገናኛ፤ ሌላም ... ፤

መ/ የኤርትራ የውስጥ መንግሥት ስልጣን፤ የውስጥ አስተዳደር፤

ሠ/ የኤርትራን የውስጥ አስተዳደር ሕግ (ኮንስቲቲዩሽን)፤

ረ/ የዩናይትድ ኔሽን ኮሚሽን እንዲሾም፤ ሥራውም የኢትዮጵያን መንግሥትና የኤርትራን ሕዝብ ሃሳብ መሠረት በማድረግ፤ እንዲሁም የእንግሊዝን አድሚኒስትሬሽን፤ የኤርትራን የውስጥ አስተዳደር ሕግ አተገባበር መከታተል፤ ይህንንም በ1952 ጉባዔ እንዲያቀርብ።

ሰ/ ፌዴራል አክቱና የኤርትራ የውስጥ አስተዳደር ሕግ በምን አኳኋን እንደሚጸድቅና ሥራ ላይ መዋል እንደሚጀምር ዝርዝሩን ማየት።

## 6.7 በዚህ በሁለት ዓመት ውስጥ ተዩናይትድ ኔሽን ኮሚሲነር ጋር ያደረግሁት ትግል

ኮሚሽነሩ የላቲን አሜሪካ ሰው /ማቴንዞ ቦሊቪ የሚባል/፤ በጣም ፕሮ ኢጣልያን ነበር። የፌዴራል አክቱን መንፈስ ሳይከተል የተቻለውን ያህል ለኤርትራ ነጻነት የሚሰጥ ሕግ ያሰናዳ ጀመር። ይኸውም ለኢትዮጵያ መንግሥት የተሰጠውን ልዩ ልዩ ሥልጣን ለኤርትራ የውስጥ አስተዳደር እየሰጠ። አሥመራ እየተመላለስኩ ሃሳቡን ሁሉ በመቃወም አንድ ባንድ አፈርስ ነበር። የሱ ሃሳብ ያሰናዳውን ሕገ-መንግሥት እንቀበልም ብለን እምቢ ስንል ኢትዮጵያኖች አልተቀበሉምና ለኤርትራ ነጻነት ይሰጥ ለማለት ነበር። ለምሳሌ፤ አውሮጳ ሄዶ ስማቸው በዓለም የታወቀ የስዊድን ጁሪስቶች ብዙ ገንዘብ ከፍሎ ሃሳብ

እንዲሰጡት አደረገ፣ በጽፌት። እሱም የሚለው፣ «ፌደራል አክቱን ለመለወጥ /ለምሳሌ፣ ፌደራሲዎኑን ሰርዞ እንዲሁ ለመቀላቀል/ ዩናይትድ ኔሽን ታልተስማማበት አይሆንም» የሚል ነበር። ጽሑፋቸው አርካይቭ ይገኛል። ይህን ጊዜ ሲመለስ አሥመራ አውሮፕላን ማረፊያ ይህንኑ በመግለጽ ዲስኩር አደረገ። ወዲያውኑ አሥመራ በአውሮፕላን ሄጀ ተኮሚሽነሩ ጋር ስብሰባ እንዳደርግ ጠየቅሁ። ስብሰባውም እንዲሆን በመንግሥቱ ስም ኦፊሲኣል ዲክሌራሲዎን አደረግሁ። ይህም ባጭሩ፣ «ሕግ አዋቂዎች ተብለው የሰጡትን ሃሳብ እንስማማም፤ በመንግሥቱም ስም እቃወማለሁ። ዩናይትድ ኔሽን ያደረገው ሬዞሊሽን ለኢትዮጵያና ለኤርትራ ሕዝብ ሪኮማንዲሽን ነው። ልንቀበለው፣ ላንቀበለውም እንችላለን፤ ግዴታ የለብንም። የተቀበልነውም ጊዜ /ያጸደቅነው ጊዜ/ እንዲሁ ተስማምተን ልንለውጠው እንችላለን። ኢትዮጵያም፣ ኤርትራም በዩናይትድ ኔሽን ሞግዚትነት አይደለም የምንተዳደረው። ነጻ ሕዝቦችና መንግሥት ነን። ይህንንም፣ ለዩናይትድ ኔሽን ራፖርህን ስታቀርብ፣ የኛንም ዲክሌሬሽን አብሮ እንዲቀርብ እጠይቃለሁ» የሚል ነበር። ተዚህ በኋላም ጉባዔው ተዘግቶ ወደ አዲስ አበባ ተመለስኩ።

ተዚህ ሁሉ በኋላ የኤርትራ የውስጥ አስተዳደር በፌደራል አክት መንፈስ ተተሠራ በኋላ፣ የኤርትራም ሕዝብ እሲምብሊውን መርጦ ታጸደቀ በኋላ፣ ጃንሆይ ፌደራል አክቱንና የኤርትራን የውስጥ አስተዳደር ሕግ አጸደቁት። ተዚያም አሥመራ ገብተው ምጽዋንም ጎበኙ፤ እኔም አብሬ ነበርኩ። በዚያን ጊዜ የኢትዮጵያን ሕዝብና የኤርትራን ሕዝብ ደስታ ለመግለጽ ቃልም አይገኝለትም። ***ስኔም በህይወቴ ሁሉ እንደዚያ ጊዜ ደስታ ሳገኝም ስልችልም***። ኤርትራን ለማግኘት የደከምኩት በሽታ ላይ ጥሎኝ በየጊዜው እታመም ነበር። በሃሳብ እንቅልፍ እያጣሁ፣ አለርጅ እየያዘኝ። የአውሮጳ ሐኪሞች ሁሉ መድሐኒት የለውም፤ ጫና የሌለበት የቬጄቴቲብ ኑሮ ለስድስት ወር ማረፍ ብቻ ነው ይሉኝ ነበር። ያደረኩት ጉዞ፣ በአውሮፕላን፣ አንድ ጊዜ ሲታሰብ ላንድ ወር ያህል (ወደ 700 ሰዓት) በሰማይና በመሬት መካከል እንደቆየሁ ነበር። ያደረኩት ዲስኩርና ኢንተርቬንሽን በሺህ የሚቆጠር ገጽ ይሆናል። ይህ ሁሉ በአርካይቭ ይገኛል። ተዚህ በኋላ ራስ እንዳርጌ የጃንሆይ ሬፕሬዘንታቲቭ ሆነው፣ አቶ ተድላ ባህሩ /ያንድነት ወኪል/ ሽፍ ኤግዚኩቲቭ ሆነው ኤርትራን ማስተዳደር ጀመርን።

## 7. አፋምቦን በምን አኳኋን እንዳስመለስኩ

አፋምቦ፣ በኢትዮጵያና በፈረንሳይ ሱማሌ ጠረፍ አጠገብ በኢትዮጵያ ውስጥ የሚገኝ ስትራቴጂክ የሆነ ሥፍራ ነው። አውሣንና የፈረንሳይን ሱማሌ ተራራማ በመሆን ኮንትሮል የሚያደርግ፣ ውሃም ያለበት በጣም ጠቃሚ ሥፍራ ነው። ፈረንሳዮች ሁልጊዜ የጅቡቲ ግዛታቸውን ለማስፋፋት ወደ አውሳና ድሬዳዋ ነበር ዓይናቸውን የሚያዘነብሉት /በ1906 ፈረንሳይ፣ እንግሊዝና ጣልያን ኢትዮጵያን በዞን ለመከፋፈል ያደረጉትን ውል ማየት ይቻላል/።

ከ1944 ውል በኋላ እንግሊዞች ኢትዮጵያን ለቀው ሲሄዱ ፈረንሳይዎች አፋምቦን መያዛቸውን ተእንግሊዞች ሰምቼ፣ የፈረንሳይን አምባሳደር ጠርቼ ፕሮቴስታሲዎን አድርጌ በቶሎ እንዲለቁ ብጠይቅ፣ «አገሩ የፈረንሳይ ስለሆነ አንለቅም» አለ። ተጃንሆይ ጋርም፣ ተመንግሥቱ ጋር ተመካከርኩ፣ በኃይል ለመውሰድ። ያን ጊዜ ራስ አበበ የጦር ሚኒስትር ነበሩ። ኃይል፣ በዚያን ጊዜ ጅቡቲ ታሉት ፈረንሳዮች ጋር ለመዋጋት የሚበቃ፣ እንደሌለ አስረዱን። ሃሳቤ ጅቡቲንም ለመያዝ ነበረ። ምንም በኃይል አለመቻሉን ሲታወቅ በዲፕሎማሲ ብቻ የተቻለውን እንዳደርግ ታዘዝኩ።

የፈረንሳይን አምባሳደር ጠርቼ፣ «እናንተም 'የኛ ነው' ስትሉ እኛም 'የኛ ነው' ስንል፣ የሚለየን በጅቡቲና በኢትዮጵያ መካከል የተደረገው የጠረፍ ውል ነው። ተውሉ ጋር የተያያዘ ካርታ፣ የሼራ ካርታ የሚባል አለ። ስለዚህ አሁኑኑ አንድ ስምምነት ፕሮቶኮል ፈርመን ዲሊሚቴሽን ለማድረግ እንስማማ፤ ይህንንም ስናደርግ አፋምቦ በውነት የማን እንደሆ ይታወቃል» አልኩት። እሱም በመንግሥቱ ስም፣ «አሁን ጦርነት ላይ ነው ያለነው፤ ይህንን ለማድረግ ጊዜም የለ፤ አፋምቦንም አንለቅም» አለ።

እኔም፣ «አገራችንን ይዛችሁ አንለቅም፤ አገሩ የማን እንደሆ ለመነጋገርና ስምምነት ለማድረግ አንድ ስምምነት እናድርግ ብንል እምቢ ታላችሁ፤ የፈረንሳይ አምባሳደርነትህን ፕሪቪሌጅ ሁሉ እንስተናል። ይህንንም የምናደርገው በመጨረሻ በኣቫል ሬገርም ጊዜ

እናንተ የኢትዮጵያን ነጻነት እናውቅም ብላችሁ የጣልያንን ይዞታ አውቃችሁ ስለነበር ነው። እናንተም በጀርመን አራት ዓመት ስለተያዛችሁ፣ የፈረንሳይን ነጻነት አናውቅም። ያቀረብኩትን የውል ሀሳብ መንግሥትህ ተቀብሎ ለመፈረም ፈቃደኛ የሆነ ጊዜ፣ ስምምነቱን ስንፈርም አንድ መግለጫ እናወጣለን፤ ይኸውም ኢትዮጵያንና ፈረንሳይ በኦፊሲል እንደ ነጻ አገርና መንግሥት የሚተዋወቁበትን። እስከዚያ ድረስ ግን እንደ ፕራይቬት ሰው ነው የምንመለከትህ» ብዬ፣ ማናቸውንም ፕሪቬሌጅ አነሳሁ። ባንዲራ D.C ኦቶሞቢሉ ላይ ማድረግ እንዲከለከል ለፖሊስ ነገርኩ። የዲፕሎማቲክ ኢሚዩኒቲ መነሳቱን ለመንግሥቱ አስታውቆ መልሱን ሲጠባበቅ ቆየ።

ተትንሽ ቀን በኋላም የፈረንሳይ መንግሥት (ደጎል) በሃሳባችን ተስማምቶ ውሉን እንዲፈርም አዘዘው። አምባሳደሩም መሲዬ ደብሊስ ይባል ነበረ። በዚህ አኳኋን ፕሮቶኮሉንም፣ ሁለቱ መንግሥት የሚተዋወቁበትም አብሮ ተፈረመ።

ያጼ ምኒልክን ውል መሠረት በማድረግ /የውሉ ዓመት 1897 እ.እ.አ/ በፈረንሳይ ሱማሌና በኢትዮጵያ መካከል ያለውን ድንበር መጀመርያ ካርታ ላይ በኋላም መሬት ላይ ምልክት ለማድረግ በሁለቱም በኩል ኮሚስዮን ተቋቋመ። በኛ በኩል አንኮሎኔል ክፍሌ እርገቱና አቶ አበበ ገብረ ጻድቅ ነበሩ /ኮሎኔል ክፍሌ አሁን ደጃዝማች፣ ያን ጊዜ የጸጥታ ኃላፊ ነበር።/

## 7.1 በሥራው ጊዜ የገጠመን ችግር

በካርታ ሥራ ምንም ፕሪሲዝን /precision/ የሌለው፣ በጣም ቬግ የሆን፣ አገሩን ሳያየው እቤቱ ቁጭ ብሎ ወሰኑ በዚህ በዚህ ስፍራ እንዲህ ያለው ስም ባለው ተራራ ያልፋል እያለ ነው ያስመረው። እቦታው ላይ ሲኬድ ፈረንሳይዎች ተብዙ ጊዜያት ጀምረው የቦታውን ስም ሁሉ ለውጠውት ተገኘ /ለነሱ ጥቅም በሚሆን አኳኋን፤ የሀይቁን ስም ጭምር ሁሉ/። ምስክሮች ቢቀርቡም ሁሉም በነሱ የተገዙና አፋምቦ የፈረንሳይ ነው እያሉ የሚመሰክሩ ሆኑ። እኛ ደግሞ የኛ መሆኑን

የሚያስረዳ እንድም ኢንስቲቱሽን ቤት፣ ሠፈር የመሰለ ያደረግነው የለም። በዚህ አኳኋን ስሙም ተለውጦ ወደነሱ ስለሚያደርገው፣ ምስክር ሁሉ የነሱ ስለሆነ፣ የምንከራከርበት መንገድ አጣን።

በዲፕሎማቲክ ታልሆነ በቀር በውሉ መሠረት የደምቡን ማግኘት የማይቻል መሆኑን ተተረዳሁ በኋላ ፓሪስ ሄድኩ። እዚያም ተጠቅላይ ሚኒስትሩ መሲረኒ ማየር /ወዳጄ ነበር/ ተገናኘቼ ሁሉንም አስረዳሁት። ፈረንሳይና ኢትዮጵያ ተድሮ ጀምሮ ያላቸውን ወዳጅነት፣ በኢትዮጵያ ባቡር የፈረንሳይን ጥቅም፣ ጅቡቲ የኢትዮጵያ ናቹራል በር መሆኗን፣ የፈረንሳይ አርኪዎሎጂ ሚሲዎን እንዲሁም የፓስተር ኢንስትቲዩትና የፈረንሳይ ሊሴ መኖር፣ ይህ ሁሉ እያለ ፈረንሳይ በአፋምቦ ምክንያት ከኛ ጋር መጣላት ጥቅም እንዳልሆነ ገለፅኩለት። እሱም በነገሩ አስብበታለሁ ብሎ ምሳም ጋብዞኝ፣ በሁለተኛው ቀን ተውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ መሲዩ ቢዶ ጋር እንድነጋገር ለሱም ትእዛዝ መስጠቱን ነገረኝ። በቀጠሮውም ተቢዶ ተገናኘተን ተነጋገርን። እሱም ወደኛ ተመልሶ ዲሊሚቴሽን እንዲደረግ መስማማታቸውን አስታወቀኝ። በንግግሩም ጊዜ አቶ አበበ ገብረጻድቅ የሚያስፈልገውን ዶኩሞመንት ይዞ ተኔ ጋር ፓሪስ ይገኝ ነበር።

በዚህ አኳኋን በፈረንሳይ ሱማሌና በኢትዮጵያ መካከል ውሉን ተከትሎ አፋምቦን ወደኛ አድርጐ የዶሊሚቴሽኑ ሥራ አለቀ (ዶክሜንቱን ማየት)። ያን ጊዜም፣ የፈረንሳይ ጋዜጦች የፈረንሳይ መንግሥት ያደረገውን ክሪቲክ አድርገው «የማይገባ አገር ለኢትዮጵያ ተሰጠ፣ ጃንሆይና አክሊሉ የፈረንሳይ ጠላት ናቸው...» የሚል ካምፓኝ አድርገው ነበር። በፓርላማም ጉዳዩ ተነስቶ ክርክር ተደርጎ ነበር /ይህ ሁሉ ፈረንሳይ አርካይቭ ይገኛል/።

# 8. ጋምቤላ ወደ ኢትዮጵያ እንዲመለስ ያደረግሁት ነጕሳሲዎን (1954—55)

በአጼ ምኒልክና በእንግሊዞች መካከል (የሱዳንና የኢትዮጵያን ድንበር በተለይ የሚወስነው) በ1902 እ.አ.አ የተፈረመው ውል የሚለው ጋምቤላ በእንግሊዞቹ እጅ ይቆያል፤ ይኸውም እንግሊዝ እሱዳን እስካለች ድረስ ነው የሚል ነበር።

በ1954 ተጃንሆይ ጋር እንግሊዝን የጐበኘን ጊዜ ለሚስተር ኤደን ጉዳዩን አነሳሁበት፤ «ሱዳን በቅርብ ጊዜ ነጻ መሆኑ አይቀርም፤ ስለዚህ በውሉ መሠረት አሁኑኑ ጋምቤላን ብታስረክቡን» በማለት። እሱም፤ «የሱዳን ነጻነት ገና ነው፤ ሁለትና ሦስት ዓመት ቢያንስ ይወስዳል። በውሉ መሠረት ሱዳንን እስከምንለቅ መጠበቅ አለባችሁ» ብሎ፤ አጥብቆ ተከራከረ። እኔም፤ «ሱዳን ነጻ መንግሥት እስኪሆን ጠብቀን በኋላ ተነሱ ወንድሞቻችን ጋር ጋምቤላን አስረክቡን እያልን መጣላት አንፈልግም /እናንተ መቼም ይህ ነው ሥራችሁ።/ ስለዚህ አሁኑኑ አስረክቡን» ብዬ አጥብቄ ጠየቅሁ። በመጨረሻም አንድ ፎርሙላ ላይ ስምምነት አድርገን ተለያየን። ይህም ሱዳን ነጻ ተመውጣቱ ከሦስት ወር በፊት ሁለቱ መንግሥታቶች ተነጋግረው ጋምቤላን እንዲያስረክቡ።

ከሦስትና አራት ወር በኋላ አዲስ አበባንና ኢትዮጵያን ለመጎብኘት ማርሻል ቲቶ ስለመጡ፤ ተሳቸውና ተጃሆይ ጋር ለጉብኝት ምጽዋ እንገኝ ነበር። በሬዲዎን ስንሰማ፤ ታምስት ቀን በኋላ እንግሊዝ ለሱዳን ነጻነቷን የሚሰጥ መሆኑን ወሬው አተተ። ሁለትና ሦስት ዓመት የተባለው ሁሉ ውሸት ሆነ። እንግሊዝ ጋምቤላን ሳትለቅ ለሱዳን አስረክባ ልትሄድ መሆኑንና፤ ተሱዳንም መንግሥት ጋር ኮንፍሊክት እንደሚሆን ግልጽ ነበር።

ጉዳዩን ለጃንሆይ አስረድቼ፤ ወዲያውኑ ወደ አዲስ አበባ መጥቼ /እርብ ቀን ነበር/፤ አንድ ኖት አሰናድቼ፤ ቅዳሚት የእንግሊዝን አምባሳደር ጠርቼ ኖቱን ሰጠሁት። የኖቱም ቃል የሚለው፤ «በውሉ

መሠረት ጋምቤላን እንግሊዞች የሚይዙት ሱዳን እስካሉ ድረስ ነው። አሁን እንግሊዞች በድንገት ሱዳንን ስለሚለቁ፣ በውሉና ተሱዳን ጋር በተስማማነው መሠረት ተሰኞ ጀምሮ /ተሁለት ቀን በኋላ/ ኢትዮጵያ ጋምቤላን ይይዛል» የሚል ነበር። እሱም ፕሮቴስት አድርጎ ለመንግሥቱ የኛቴን ቃል አስተላልፋለሁ አለ። ለሱዳን የውስጥ አስተዳደር ባለስልጣኖችም አንድ ቴሌግራም በአቶ መለሰ አንዶም በኩል /ያን ጊዜ የኛ ሊኢዞን ኦፊሰር አሁን ካይሮ አምባሳደር/ ላክሁ። ይኸው የሚለው፣ ለነጻነታችሁ ጥልቅና መልካም ምኞታችንንና ወደፊትም እንደወንድማማቾች አብረን እንድንሠራ፣ ጋምቤላ በኮሉኒአሊስቶች በኃይል ተይዞብን ስለነበረ ተሰኞ ጀምሮ እኩፓይ ማድረጋችንን፣ ግን ይህ ወዳጅነታችንን የማይነካና የሱዳንም ቆንሲልና ማናቸውም ቤትና ኢንስቶሌሽን ቢኖር ለጊዜው ለመቆየት መቻሉን የሚገልጽ ነበር። እነሱም በነጻነታቸው ለጊዜው በደስታ የተጥለቀለቁ ስለሆነ፣ ተምስጋና ጋር በምናደርገውም መስማማታቸውን የሚገልጽ መልስ ሰጡ።

እንደተባለው ሰኞ ባትራቢያው የሚገኘው የፖሊስ ኃይል ጋምቤላ ገብቶ የኢትዮጵያን ባንዲራ አውለበለበ፤ አድሚኒስትሬሽኑንም ያዘ። ምንም አክሲደንት አልደረሰ።

ተሦስት ወር በኋላ በውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የሚመራ የሱዳን ዴሊጌሽን ጋምቤላ ስላላቸው ኢንስቶሌሽን ለመነጋገር አዲስ አበባ መጡ። በንግግራችንም ጊዜ በቁጣ መልክ፣ «ለእንግሊዞች የፈቀዳችሁትን ጋምቤላን ለምን ለኛ ላፍሪካኖች ትነፍጉናላችሁ? ጋምቤላን መልሱልን» በማለት **ከሥረ ነገሩ** መግባት ጀመሩ። እኔም፣ «እንግሊዞች ኮሉኒያሊስቶች አፍሪካን በሚከፋፈሉበት ጊዜያት በኃይል የያዙብን ነው፤ አሁን ኮሉኒ ሁሉ ነጻ ይውጣ ሲባል እናንተ ይህን እንዴት ትጠይቃላችሁ? ይልቅስ በወንድማማች መንፈስ የምትወስዱትን ዕቃ ዝርዝር ብንነጋገር ይሻላል፤ ስትመጡም በዚህ ብቻ መሆኑን የተለዋወጥነው ኖት ያስረዳል። ተዚያ በቀር ሌላ ጉዳይ ለመነጋገር የተስማማንበት ፕሮሲጀር አይፈቅድም» አልኳቸው። እነሱም ተቆጥተው ስብሰባውን ጥለው ወጡ /ያን ጊዜ ተኔ ጋር ብላታ ዳዊት፣ ምክትል ሚኒስትር እንዳልካቸውና ዋና ዲሬክተሩ ነበሩ/። በዚሁም እንዳልካቸው

ደንግጦ፣ ምን ይሆን ብሎ ጠይቆን ነበር። ግድ የለም፣ አሁን እንስማማለን ስለው፣ «እኔ መቼም ኤክስፒሪያንስ የርስዎን የለኝም» ብሎ አደነቀ። ተወጡም በኋላ ለእንግሊዝ፣ ለአሜሪካን አምባሳደሮቹ እየዞሩ ስሞታቸውን ያቀርቡ ጀመር። በኋላም እሱን [ሚኒስትሩን] ለብቻው ጠርቼ፣ በረጅሙ አስረድቼው፣ ተቆጣው ተመለሰ። አስፈላጊውን ስምምነት አደረግን። ተዚያ በኋላ የጋምቤላ ጉዳይ በሱዳኖች ተነስቶም አያውቅ።

# ፱. በኢትዮጵያና በኬንያ መካከል የሚወሰነውን ወሰን በውሉ መሠረት በምን አኳኋን እንዲከለል እንዳደረግሁ

እውጭ ጉዳይ እንደገባሁ፣ የኢትዮጵያን ወሰን ተሌሎቹ አገሮች ጋር በኢንተርናሽናል ውል መሠረት በትክክል መወሰን ዋና ጉዳይ አርጌ ነበር ያየሁት። ይህም በወልወል በደረሰብን ኤክስፔሪያንስ ነው። ተዚያም በኋላ ያፋምበ መጣ። ትንሽ መንግሥት እንደመሆናችን መጠን የተከበብነው፣ ያን ጊዜ፣ በንኛው በኮሎኒያሊስቶች ስለሆነ አጥራችንን ደህና አርጐ ማጠር አስፈላጊ ነበር። ብዙ ጊዜ የወሰኑ ውል፣ ታጼ ምኒልክ ጋር /1897—1908 እ.አ.አ/ የተደረገው ቬግ የሆነ፣ ፕሪሲዠን የሌለው ነው። ኢትዮጵያ ተመወረሯ በፊት /1935/ ታንድ አገር ብቻ ነበር ወሰናችን የተከለለው። ይኸውም ተእንግሊዝ ሱማሌ ጋር ነው። በዚሁ ምክንያት ነው ተጉረቤት አገር ጋር በየጊዜው የፍሮንቲእር ኢንሲደንት የነበረን /ቢሺን፣ በኬንያ በኩል ተናንተ ጋር ስላለው የድንበር ግጭት ፕሮቴስታሲዎን ያደረግንበት ወረቀት ይህን ቤት ይሞላል ብሎኝ ነበር/።

ይህን ሁሉ ለጃንሆይ ታስረዳሁ በኋላ መጀመሪያ ጊዜ ሉንዶን ስሄድ /በ1946/ አንዱ ጉዳይ የተነጋገርሁበት ይህ ነበር። /ተኔ ጋርም ጸሐፊ ትእዛዝ ተፈራወርቅ ነበሩ።/ ዲሊሚቴሽን ለማድረግ የእንግሊዝ መንግሥት ተስማምቶ፣ ይህንኑ ለመነጋገርና አንድ ፕሮቶኮል ለመፈራረም በቅርብ ጊዜ አንድ ዴሊጌሽን ወደ አዲስ አበባ እንደሚልክ አስታወቀ።

የእንግሊዝ ዴሊጌሽንም ተመጣ በኋላ፣ ውሉን መሠረት በማድረግ ካርታ ላይ መስመሩን ለማስመተር፣ አንድ ተእነሱና ተእኛ የተዋጣ ሚክስድ ኮሚስዎን ተቋቋመ። ሥራቸውንም ጀመሩ። ተእኛ በኩል እነ ኮሎኔል ክፍሉ፣ አቶ አበበ ገብረጻድቅና ሌሎችም ነበሩ። ብዙ ጊዜም ሥፍራውን እየሄዱ ይጉብኙ ነበር። በመጨረሻም የተስማሙበትን መስመር ለየመንግሥታቸው አቅርበው ተፈቀደ።

ተዚህም በኋላ መሬቱ ላይ ዲሊሚቴሽን ተጀመረ። ብዙ ዓመትና ብዙ ገንዘብም ተፈጀ በኋላ ሥራው አለቀ። ተትንሽ ዓመት በኋላ ቀደዱማ የሚባለው የውሃ ጉድጓድ ሕዝቡ ጠቃሚያችን ነው፣ እንደ

እድባርም የምንቆጥረው ነው ብሎ እቤት ስላለ ጉዳዩ እንዲታይ ተደረገ፣ በኮሚስዮን። የጉድጓዱ አከፋፈል የሚበልጠው ወደኛ እንዲሆን /ዘጠኝ ሥፍራ ያለው ጉድጓድ/፣ ለነሱ ደግሞ ሁለት ሥፍራ ያለ ጉድጓድ ነበር። ሃሳቡ፣ ውሃ እናጣለን በማለት የእኛም የነሱም ሕዝብ ወሰን እንዳያልፍና ኢንሲደንት እንዳይነሳ ነው። በዚሁ ጉዳይ የሕዝብ ስሜት ስላለበት ቀደዱማን እንዲመልሱ ለእንግሊዞች አስረዳኋቸው። እነሱም፣ «የሚበቃ ውሃ ተኛ ይበልጥ አላችሁ፣ ግን ኢንሲስት ታደርጋላችሁ፣ በሱ ፋንታ የሰጠነውን ያገር ክፍል መልሱና እኛም ቀደዱማን እንመልስ» ብለው፣ ጥያቄያችንን በጉድ ፈገ ተቀበሉ። በዚሁ አኳኋን ጉዳዩ ተፈጽሞ የዚያን ክፍል እንደገና መሬቱ ላይ ምልክት እንዲደረግ ሆነ።



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ከኬንያው ፕሬዚዳንት ጆሞ ኬንያታ ጋር ሲወያዩ።

ተዚያም ታመታት በኋላ ኬንያ ነጻ ስትወጣ፣ ድንበራችን ተከልሎ ስለቆዩ፣ ተኋ ጋር በወዳጅነትና በወንድማማች መንፈስ እስታሁን እንኖራለን። ተፈረንሳይ ሱማሌ ጋር ያለን ወሰን እላይ በተባለው አኳኋን ስለተወሰነ፣ ተእንግሊዝም ሱማሌ ጋር ያለው ተጦርነቱ በፊት አለቀ። ተኬንያም ጋር በዚህ አኳኋን ሲያልቅ የሚቀረን ተጣልያን ሱማሌና ተሱዳን ጋር ያለው ድንበር ነው።

ተጣልያን ሱማሌ ጋር ያለንን ለመወሰን፣ ገና ሱማሌ በዩናይትድ ኔሽን ሞግዚትነትና በጣልያን አስተዳዳሪነት ባለች ጊዜ /ተ1950—1960/ የዩናይትድ ኔሽን ሪዞሊሽን እንደሚያዘውና በስም መሠረት ለመወሰን፣ ተጣልያኖች ጋር ብዙ ጉባዔ ተደርጉበታል። ብዙም ተደክሟል። ያን ጊዜ የኛን ዲሊጌሽን፣ ስለወሰኑ ጉዳይ የሚነጋገረውን፣ የሚመራው አቶ ሐዲስ ዓለማየሁ ነበር። ጉዳዩም የደረሰበትን ለዩናይትድ ኔሽን በየጊዜው እየቀረበ ሪዞሊሽን ይደረግበት ነበር። ጣልያኖች የውሉን ትርጉም በማይገባ እየሰጡ ጉዳዩን ያጓትቱት ነበር። ያልተስማማንበትን፣ በሪዞሊሽኑ መሠረት ወደ አርቢትሬጅ ለመሄድ፣ ብዙ ታክቲክና ሳቦታጅ እያደረጉ ጉዳዩን ይጎትቱት ነበር /ሁሉንም ለመረዳት ፕሮሲቬርባሉንና የዩናይትድ ኔሽንን ዶኩሜንት ማየት ያስፈልጋል/። ለዚህ ሁሉ አቤቱታችንን ለዓለም ማህበር ማቅረብ አላቋረጥንም። ጉዳዩም ሳያልቅ ሱማሌ በ1960 ነጻ ወጣች። ጣልያኖች ጉዳዮን የሚጎትቱበትን አንድ ምክንያት ሱማሌዎችንም በመፍራት ነበር።

ሱማሌ ነጻ ተወጣች በኋላ ወሰኑን ለመከለል በየጊዜው ፕሮፖዛል አቅርበንላቸው ነበር። የነሱም መልስ፣ «ኦጋዴን የኛ ስለሆነ አንዋሰንም» ነው። በሱዳን በኩል ያለውን ብዙ ጊዜ ተተነጋገርን በኋላ በመሠረቱ ስምምነት ላይ ደርሰናል /ዶኩሜንቱን ማየት/።

## 10. የ1948 /1955 እ.ኤ.አ/ ሕገ-መንግሥት እንደምን እንደተሠራና ለዚህ የደከምኩት

ለኤርትራና ለሌሎችም ጉዳዮች በምንሟገትበት ጊዜያት የድሮው ሕገ-መንግሥት /1930/ እንዲተካ በየጊዜው ለጃንሆይ ሃሳብ አቀርብ ነበር። ይኸውም፡-

ሀ/ ሕዝቡ እየቀደመ በሄደ ቁጥር ቀድመን ተስማሚውን ያስተዳደር መሠረት የሆነውን ማሻሻል እንዳለብን፤ የበፊቱ ሕገ-መንግሥት ለጊዜው ጠቅሟል፤ አሁን ግን ጊዜው አልፎበታል።

ለ/ ተጦርነቱ በኋላ ብዙ ለውጥ በዓለም ላይ ስለሆነ ለዚህ ለውጥ ተገቢ ሆነን እንድንገኝ።

ሐ/ ሞደርንና ዲሞክራቲክ የሆነ ሕገ-መንግሥት ያለን እንደሁ በዓለም ፊት ደህና ኢምፕሬሽን ሰጥቶ ለጥያቄአችን ስለሚረዳን። ጃንሆይ ሃሳቡን ቢረዱትና ቢቀበሉትም ብዙ ሬዚስታንስ ነበር፤ ተራሶቹና ተመኳንንቶቹ በኩል፤ ማን ጠየቀንና ነው በማለት።

በመጨረሻም ተብዙ ክርክርና ሬዚስታንስ በኋላ ይህንን የሚያስረዳ አንድ ኮሚሲዮን ተቋቋመ። አባሎቹም ቢትወደድ መኩንን፣ ጸሐፊ ትእዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ አቶ ይልማና እኔ አራቱ ነበርን። ከነዚህ አባሎችም ውስጥ የሕግ ትምህርት ያለኝ እኔ ብቻ ነበርኩ። ተውጭ አገር ሕግ አዋቂዎች ሙሴ ስፒንሰር ሁል ጊዜ አብሮን ነበር። አልፎ አልፎ አንድ የውጭ አገር ስፔሻሊስት እየመጣ የተሠራውን እያየ ሃሳብ ይሰጥ ነበር።

ኮሚሲዮኑ የሚሠራው ቀጥሎ ባለው አኳኋን ነበር። እኔና ሕግ አዋቂዎቹ ያሰናዳነውን ለኮሚሲዮኑ እናቀርብ ነበረ። ተዚያም ልዩ ልዩ ክርክር ተደርጎ፣ የሚሰጡትን ለውጠው፣ ፕሮግሬሲቭ የሆነውን አስቀርተው ተተስማሙ በኋላ የኮሚሲዮኑም ሃሳብ ለዘውድ ምክር ቤት በጃንሆይ ሰብሳቢነት፣ ልዑል አልጋወራሽ ራስ ካሣ ያሉበት ቀርቦ ብዙ ክርክር ይደረግ ነበር። እያንዳንዱ አንቀጽ ለምን እየተባለ ሬዚስታንስ ሲደረግ የሌላውን አገር እየጠቀስኩ አስረጂው እኔው ነበርኩ /ዝርዝሩ

ብዙ ነው፣ ፕሮሲቬርባሉን ማየት ይጠቅማል/። በኋላም ለያንዳንዱ አንቀጽ ምስክር አቅርብ የሚል ጥያቄ ራስ ካሣ አመጡ። የ50 ያህል መንግሥታት ሕገ-መንግሥት አምጥተን የኛን አንቀጽና ሌላውን ለምስክርነት እናቀርብ ነበር። ይህ ሁሉ በዶክሜንት ውስጥ ይገኛል።

በጠቅላላው ከላይ እንደተባለው ማንንም አይጠይቀን፣ ለምንድነው የምንለውጠው በማለት ፕሮግሬሲቭ የሆነውን ሁሉ ሃሳብ ሲያከሽፍብን በብዙ ትግል አሁን ያለውን ሕገ-መንግሥት ለመሥራትና ለመጨረስ ስምምነት ላይ ተደረሰ። ጃንሆይ ሁል ጊዜም ድጋፋቸውን እንደሰጡን ነበር፣ «ልብ አርግ፣ ይህ ሁሉ ተቃዋሚ እያለ አንተን እምነን ነው ይህን ሕገ-መንግሥት የምናወጀው»፣ ሲሉ አስታውሳለሁ። እኔም አመስግኜ ለዚያን ጊዜ ለኢትዮጵያም፣ ለጃንሆይም ታሪክ አስፈላጊ መሆኑንና ደግሞ ለወደፊት እየታየ፣ ጊዜውን እየተከተልን የበለጠ ዲሞክራቲክ የሆነ ሕገ-መንግሥት ማወጅ እንዳለብን፣ ይህንንም በማድረጋችን ጥቅም እንጂ ጉዳት እንደማይኖር አረጋግጬ፣ በኃላፊነትም ጃንሆይ እንዳይዘኑ አንድ ማስታወሻ ጽፌላቸው ነበር። /አዲሱ ሕገ-መንግሥት ምንም በሙሉ ዲሞክራቲክ ነው ባይባልም - ይኸም ሬዚስታንስ ስላገኘን ነው—የመጀመሪያውን **በብዙ ለውጦታል**/።

በመጨረሻም የሕገ-መንግሥቱ ሃሳብ ለፓርላማ ቀርቦ ምክር ቤት ተተስማማበት በኋላ፣ በጥቅምት 24 ቀን 1948 /4 ኅዳር 1955 እ.ኤ.አ./ ታወጀ። ይህም በመቅድሙ ላይ ጃንሆይ እንዳሉት፣ ተብዙ ዓመታት ሪቪውና ምርመራ በኋላ ነው። በማስታወሻ በገለጥኩት መሠረት፡-

ሀ/ በአሥራ ዘጠኝ መቶ ሃምሳ ዘጠኝ ይህ አሁን ያለው ሕገ-መንግሥት እንዲሻሻል ሃሳብ አቅርቤ ኮሚሲዮን ተቋቁሞ ሃሳቡ ለጃንሆይ ቀርቧል፤

ለ/ አሁንም በቅርቡ፣ እኛ ሥራ ተተውን በኋላ፣ ሕገ-መንግሥቱ እንዲለወጥ ሃሳብ አቅርቤላቸው ነበር። ይህንንም እንደግል ኢትዮጵያዊነቴ፣ ማንም ሃሳቡን ለማቅረብ እንደሚችል እንጂ በሌላ በሥራም ሆነ አንድም ሃሳብ የሰጠሁትና ኢንተርቪን ያረኩት የለም። ሃሳቡንም ራሳቸውም አስበውበት ለሕዝቡ በራዲዮን ገለጡት።

## 10.1 የፍትሐብሔር፣ የወንጀለኛ፣ የንግድና የባሕር ሕጎች

ሕገ-መንግሥቱ ተቃወጀ በኋላ፤ ይህንኑ ተከትሎ ተስማሚ የሆነ የፍትሐ ብሔር፣ የወንጀለኛ፣ የንግድና የባሕር ሕጐች /Code Civil, Code Penal, Code Commercial, Code Maritime and Code Procedure/ ማሰናዳትና ማወጅ አስፈላጊና ጠቃሚ መሆኑን ለጃንሆይ ሃሳብ አቀረብኩ። እሳቸውም ሃሳቤን በሙሉ ተቀብለውት፤ ይህም ታላላቅ ሊቃውንትና ሕግ አዋቂዎች ማስፈለጉን፤ ማሰናዳቱ ብዙ ጊዜም እንደሚፈጅ ገምቼ ነበር። ለዚሁም አውሮፓ ሄጄ ሪሰርች ታደረግሁ በኋላ በዓለም የታወቁ ስፔሻሊስት የሆኑትን በመጠየቅ፣ ተነሱም በመነጋገር፣ ለፍትሐብሔር ሕግ ፕሮፌሰር ዳቪድ፣ የሶርቦን ዩኒቨርሲቲ የዚሁ ክፍል አስተማሪ፤ ለወንጀለኛ የስዊስ ዩኒቨርሲቲ አስተማሪ ፕሮፌሰር፤ ለንግድ ሕግ በሶርቦን አስተማሪ የሆነ ፕሮፌሰር እንዲቀጠር ሆነ። እነሱም አዲስ አበባ መጥተው ተኢትዮጵያ በኩል ተተቋቋመው ኮሚሲዎን ጋር ስራቸውን ጀመሩ። የኢትዮጵያን ኮሚሲዎን አባሉችም ሆኑ።

ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር /ኅዳር 1950—1957/ በዚህ በሦስት ዓመታት ጊዜያት ምንም ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትር ብባል በሚኒስትሮች ምክር ቤት ሰብሳቢና ፕሬዚዳንት ራስ አበበ አረጋይ ነበሩ። እዚያ የተወሰነውንና በጃንሆይ የጸደቀውን ትእዛዝ ማስተላለፍ ብቻ ነበር፣ ዋና ሥራዬ። በሌላ በኩል ደግሞ የውጭ ጉዳይ ሥራ ነበረብኝ። ቢሆንም፣ በዚያን ጊዜ ነው ከላይ የተዘረዘሩት ህጎች የወጡት።

## 10.2 ጠቅላይ ሚኒስትርና የጽሕፈት ሚኒስትር መጋቢት 23/1959

ጠቅላይ ሚኒስትርም የሆንኩት ተኩዶ-ታ በኋላ ነው። ወዲያውኑ በብዙ ክፍል ልዩ ልዩ ሪፎርም ማድረግ አስፈላጊ መሆኑና አሁንም ኢትዮጵያ ለደረሰችበት ተገቢ መሆኑን በየጊዜው ለጃንሆይ ሃሳብ እያቀረብኩ፤

ስለሚደረገው መሻሻል በየጊዜው ተነጋግረን ጃንሆይ በመሠረተ ሐሳቡ ተተስማሙ በኋላ፣ ያንጊዜ ኮሊግ ተሆኑት ጀኔራል አቢይ፣ ያገር ግዛት ሚኒስትር፣ ጀኔራል መርድ፣ የመከላከያ ሚኒስትር፣ አቶ ይልማ፣ የገንዘብ ሚኒስትር የነበሩትን አነጋገርኩ። እነሱም በሃሳቡ ተስማሙበት፣ በኋላ የዚህን ሪፎርም ሃሳብ የሚዘረዝር አንድ ማስታወሻ አስናድቼ አብረን ለጃንሆይ እንድናቀርብ አደረግሁ። እሳቸውም መፍቀዳቸውን ገለጡልኝ፣ ሐምሌ 8/1953።

እንዲሻሻሉ ያቀረብኋቸው ዋና ዋና ጉዳዮች ቀጥሎ ያሉት ነበሩ።

1. የሕገ-መንግሥት የሚሻሻልበትን፣
2. የፍርድ ሥራ የሚሻሻልበትን፣
3. የመሬት ይዞታ የሚሻሻልበትን፣
4. የጠቅላይ ግዛቶች የውስጥ አስተዳደር የሚሻሻልበትን፣
5. የአገር አገዛዝ ደንብ አስተዳዳር የሚሻሻልበትን፣
6. የአድሚኒስትራሲዎን ሥራ የሚሻሻልበትን፣
7. የጠቅላይ ሚኒስትርና የሚኒስትሮች ሥልጣን፣
8. ትምህርት የሚስፋፋበትን፣
9. የመንግሥት ሠራተኞች አስተዳደር፣
10. የአሠሪና የሠራተኞች ግንኙነት ሕግና የሠራተኞች መሥሪያ ቤት መቋቋም፣
11. የመንግሥት ሠራተኞች የጡረታ ሕግ፣
12. የወንጀለኛና የብሔራዊ ሕግ ሥነ-ሥርአት፣
13. የአምስት ዓመት ፕላንና
14. የጥቅም መጋጨት።

እነዚህን ከላይ የተዘረዘሩትን ጉዳዮች እያጠና ሃሳብ የሚያቀርብ በጠቅላይ ሚኒስትር ሥር የሚኒስትሮችና ተገቢ የሆኑ የመንግሥት ሠራተኞች የሚገኙበት፣ ሰባት ወይም ስምንት ኮሚሲዎኖች ተቋቋሙ፣ ዝርዝሩን ዶክሜንቱን ማየት።

የበላይ ኮሚቴ፣ በኔ ሰብሳቢነት፣ አባሎቹ እነጀኔራል አቢይ፣ ጀኔራል መርድ፣ አቶ ይልማ፣ **የሕገ-መንግሥት መሻሻያ** ኮሚሲዎን

ስብሳቢ አቶ አበበ ረታ፣ አባሎች ኮሎኔል ታምራት፣ ልጅ እንዳልካቸው፣ አቶ ማሞ፣ አቶ ከተማ፣ ደጃዝማች ሥዩም፣ አቶ ጌታቸው ክብረት፣ ሚስተር ፓራዲስ ነበሩ። ሌሎችም ይህ የመሰሉ አባሎች የነበሩበት ነው። ለምሳሌ፣ የመሬት ማሻሻያን መጀመሪያ ኮሎኔል ታምራት፣ ቀጥሎም አቶ ታደሰ፣ በኋላም አቶ አካለ ወርቅ ነበሩ የሚሰበስቡት።

ኮሚሲዮኖቹ ሥራቸውን አንድ ምዕራፍ በደረሱ ቁጥር ተበላይ ኮሚቴ ጋር ስብሰባ ተደርጎና ሃሳብ ለሃሳብ እንለዋወጥ ነበር። የኮሚቴውና የኮሚሲዮኖች ስብሰባ በየጊዜውም በጋዜጣና በራዲዮን ይወጣ ነበር።

የሕገ-መንግሥት ኮሚሲዮን ሥራውን ሠርቶ ይሻሻል ብሎ ያቀረበው ማስታወሻ ቀርቦልን ተተንጋገርንበት በኋላ ተስማምተንበት ለጃንሆይ አቀረብን፣ ፋንዳሜንታል የሆነ የሃሳብ ለውጥ አላቀረቡም ነበር። /ማስታወሻቸውን ማየት።/

ሌላው ኮሚሲዮኖች የሚያቀርቡትን በዚሁ አኳኋን እየሠራን ለጃንሆይ እናቀርብ ነበር። ብዙም ጊዜ ጃንሆይ ዘንድ፣ የዘውድ ምክር ቤት አባሎችና ሌሎች ሚኒስትሮች ያሉበት፣ ስብሰባ እየተደረገ የተወሰኑ አሉ፣ ፕሮሲቨርባሉን ማየት።

**በዚህ አኳኋን ጠቅላይ ሚኒስትር በነበርኩበት ጊዜ ያለቁትና የተፈጸሙት፡-**

1. የሁለተኛና የሦስተኛ የኢትዮጵያ ያምስት ዓመት ፕላን፣
2. የመንግሥት ሠራተኛ ጡረታ ሕግና ደንቦች፣
3. የመንግሥት ሠራተኞች ማስተዳደሪያ ሕግና ደንብ፣
4. ያሠሪና ሠራተኞች ግንኙነት ሕግ፣
5. ያውራጃ የውስጥ አስተዳደር ትእዛዝ /ሕጉን ፓርላማ ለማውጣት ስላልፈቀደ/፣
6. የሕዝብ ልማት ድርጅቶች /ኮኦፕሬቲቭ/ አቋሞች ደንብ፣
7. የመሬት ይዞታ ጉዳይ፣ የጉልት መቅረት፣ የጢሰኛና የባለርስት ግንኙነት ሕግ በፓርላማ ለማቅረብ በየጊዜው ክርክር ላይ ነበር። ፓርላማ ይህን እስታሁን ለማውጣት ባለመፍቀዱ፣ ሌላው የመሬት

መያዣ ጣሪያና ሬጅስትሬሽን ተሰናድቶ ነበር። በመሬት ይዞታ ሚኒስቴር የተሰናዳውን ሁሉ ማየት።

8. ያገር አገዛዝ ደንብ፤
9. የፍርድ፣ የዳኞች አሿሿምና ነጻነት ሕግ፤
10. የፍትሐብሔርና የወንጀለኛ ሕግ ሥነ-ሥርዓት፤
11. የሚኒስትሮችና የጠቅላይ ሚኒስትር ሥልጣንና ተግባር፤
12. የሚሊቴሪ ሰርቪስ ሕግ ናቸው።

## 10.3 የአፍሪካ አንድነት ድርጅት

1. ይህን ድርጅት ለማቋቋም የተደከመው ዝርዝሩ ብዙ ስለሆነ ባጭሩ ብቻ እጠቅሰዋለሁ።

   ሀ/ አፍሪካ በሦስት ግሩፕ ተከፋፍሎ ነበረ፤

      1. የካዛብላንካ ቡድን፣
      2. የሞንሮቪያና
      3. የአረብ ሊግ።

   ለ/ የመጀመሪያው ስብሰባ በሌጐስ በ1961 እንዲሆን አደረግን። በዚህም የኢትዮጵያ ሮል ብዙ ነው፤

   ሐ/ በስብሰባው ጊዜም እኛ ብቻ ነበርን በቋንቋችን የተናገርነው። ሌሎቹ በእንግሊዝ፣ በፈረንሳይና በአረብ ነበር። ቻርተሩን ለመሥራትና ለመፈራረም አዲስ አበባ እንዲሆን ብዙ ደከመን ስለነበረ በዚሁ ተወሰነ።



የናይጄሪያውን ፕሬዚዳንት (ጀነራል) ያኩቡ ጎዋን ለአፍሪካ አንድነት ድርጅት ስብሰባ አዲስ አበባ የመጡ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ሲቀበሏቸው።

መ/ የአዲስ አበባ ስብሰባ 1962

- ተስብሰባው በፊት የቻርተሩን ድራፍት /ሃሳብ/ እኔ ቢሮ አሰናዳን፤ ተሳቲን አሜሪካ አንድ አዋቂ ቀጥረን ነበር/።
- የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮች ሲሰበሰቡ ድራፍቱን አቀረብን።
- የነሱ ሃሳብ፤ መሪዎቹ ተስምንት ቀን በኋላ ሲሰበሰቡ እንዲያጠኑትና ሃሳብ እንዲሰጡበት፤ ለሚመጣው ዓመት ለማስተላለፍ ነበር።

- ዋናቹን /የግብጽ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ዶክተር ፋውዚ፤ የኔ የድሮ ወዳጅ ስለነበረ /በየተራ ጋብዤ አሁኑኑ መፈረም አለብን እያልኩ አግባባኋቸው።
- የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮቹ በድራፍቱ ተስማምተውበት፤ የመሪዎች ጉባዔ ተከፈተ።
- መሪዎቹ ዲስኩራቸውን በሚያደርጉበት ጊዜያት፤ የውጭ ጉዳይዎቹ በኮሚሲዮን ተሰይመው ድራፍቱን እንዲአዘጋጁ አደረግን /አምስት ቀን ብቻ ስላለ/። ጃንሆይም፤ «ይህን ሳንፈርም መሄድ የለብንም» ብለው እንዲናገሩ ተደርጎ ሌላውም ተከተለ።
- የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮች ጉባዔ ራፖር ቀረበ፤ ክርክር ተደረገ።
- አሁን መፈረም አይቻልም ያሉትን አግባባናቸው።
- ሌሊት በ11 ሰዓት ተፈረመ።

2/ የመጀመሪያው የድርጅቱ ስብሰባ ካይሮ በ1963 እንዲሆን ተወሰነ።
- ሄድኳርተሩ አዲስ አበባ እንዲሆን እዚያ ድረስ በልዩ ልዩ መንገድ ሥርተን ነበር።
- ስብሰባው እንደተከፈተና በዲቤቱ ጊዜያት፤ የድርጅቱ ሥፍራ አዲስ አበባ እንዲሆን ሃሳብ አቅርቤ በጭባጨባ ተቀበሉት።
- በዚህም ጊዜ ያገሮቹ ወሰን ሁሉ፤ በተሰቀቁ ጊዜያት ባለው እንዲረጋ ተወሰነ።

3/ ድርጅቱ ለኢትዮጵያ የሰጠው ጥቅም፤

ሀ/ ኢኮኖሚክ
- የተከፈተው ኤምባሲ ወደ 70 ደረሰ፤
- አዲስ የጉባዔ መሰብሰቢያ ሆነ፤
- የሥራ ዕድል ከፈተ፤

ለ/ ፕሬስቲጅ፤ ልዩ ልዩ ድርጅቶች ሥራቸውን እዚህ አቋቋሙ፤

ሐ/ ፖለቲካ፤ በሱማሌ ያደረግሁት ኢንተርቤንሽን።



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ በ1963 የአ.አ.ድ ስብሰባ ላይ።

የዩናይትድ ኔሽን የኢኮኖሚክ ድርጅት አዲስ አበባ መሆኑ ተዋናቹ መንግሥቶች /ተአሜሪካ፣ ተእንግሊዝና፣ ተፈረንሳይ/ ጋር በንግግርና በመግባባት ያደረግሁት ቀደም ብሎ ነው፤ ዝርዝሩ ብዙ ነው።

## 10.4 ስለመከላከያ መሣርያ ለማስገኘት የደከምኩት

1/ ተአሜሪካኖች ጋር **የመረዳዳት ውል** /Mutual Assistance Agreement/ በ1953 እንደምን እንደተከራከርኩና እንደፈረምኩ፦

ሀ/ 12,000 /አሥራ ሁለት ሺህ/ ጠመንጃ ለመግዛት እንዲፈቀድልን ነበር፤ ለመነጋገር ተጃንሆይ የተላክሁት። ያንጊዜ በገንዘባችንም ቢሆን መሳሪያ ለመግዛት አይፈቀድልንም ነበር።

ለ/ ዋሽንግተን እንደደረስኩ በመጀመሪያ ተፕሬዝዳንት አይዘናወር ጋር ታልተነጋገርኩ፤ ተሌላ አልነጋገርም አልኩ። ይኸውም፤ ሁሉንም ከላይ ለመጀመርና ለማስረዳት ነበር። እነሱ ግን እምቢ ብለው አምስት ቀን ቆየን። ይህንንም ያደረግሁት ለጉዳዩ ኢምፖርታንስ እንዲሰጡት ነው።

ሐ/ ፕሬዝዳንቱን ተቀብሎኝ ጉዳዮቻችንን በረጅሙ አስረዳሁት /ዝርዝሩ ብዙ ነው/፤ ኢምፕሬስ ሆነ።

መ/ እሱም ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ዳላስ፤ እኔው ፊት ደውሎ፤ በቀጠሮው ስማው ብሎ ሪኮማንድ አደረገልኝ።

ሠ/ ተዳላስ ጋር ስንነጋገር በፊት በሰላም ጉባዔ ጊዜ የተነጋገርነውን አስታወስኩት፤ አትሞስፈሩም ደህና ሆነ፤ አስረዳሁ። እሱም፤ «እኛ ይገባናል፤ ግን ፔንታጎንን ነው ኮንቪንስ ማድረግ» አለኝ። እኔ የማኘሁን ነገር ትቼ፤ በርዳታ መልክ እንዲያደርጉልኝ ነበር የጠየቅሁት። ጀነራል ሙሉጌታ እንዲረዳኝ አስመጥቸው ነበር፤ ሁለታችን ብቻ ነበርን።

ረ/ ፔንታጎን እንዳስረዳ፤ ስቴት ዲፓርትማ አሰናድቶ፤ ትልቅ ስብሰባ ተደረገ፤ ብዙ ጀነራሎች ያሉበት። እነሱም ተብዙ ጥያቄና መልስ በኋላ ኢምፕሬስ ሆነው ፊቬሬብል መልስ ሰጡ።

ሰ/ ተስቴት ዲፓርትመንት ጋር ንግግሩ ቀጠለ።

ሀ/ የሚግ ጉዳይ ንግግር፤

ለ/ በያመቱ የሚሰጡን የመሣርያ እርዳታና

ሐ/ ቤዝ ጉዳይ /አሥመራ ያለው የቴሌኮሚኒኬሽን ሴንተር/።

ተዚህ በኋላ ሁለት ስምምነት ተፈረመ፤

- የእርዳታውና
- የአሥመራ የቴሌኮሚኒኬሽን ሴንተር። የጃንሆይ የፊልስቴሽን ቴሌግራም፤ ለኔ የተደረገ፤ አርካይቭ ይገኛል። ይህ ሁሉ መሣርያ ደክሜ ያመጣሁት መሆኑን ታሪክ ያስረዳል።

2/ መሣርያችንን በርዳታ ለመጨመር በየጊዜው የተደረገው ድካም

ሀ/ የጀነራል መርድ ጉብኝት በኩባ ክራዚ ጊዜያት

ለ/ በ1966 ጃንሆይ ያደረጉት ጉብኝት

- ተፕሬዝዳንት ኬኔዲ ጋር
- ሚሞራንደም
- ውጤት - F 5 – 8
- For training 2000 1b
- በ 66 ተፕሬዚዳን ጆንሰን ጋር። የነበሩት፡-
- ጀነራል ወልደ ሥላሴ፣ አቶ ከተማ፣ ዶክተር ምናሴ።
- በ 70 ከNixon ጋር። የነበሩት፡-
- ጀነራል ከበደ፣ ማሞ፣ ከተማ፣ምናሴ
- በ 73 ከNixon ጋር። የነበሩት፡-
- ጀነራል ከበደ፣ ጀነራል አሰፋ፣ ምናሴ ውጤት - እናጠናለን።

3/ ስለ ኡጋዴን ጉዳይ

- አጥንቶ እንዲያቀርብ (Conseil de defence 64?)
- ጀነራል ከበደ
- አሰፋ
- ድረሴ
- ገንዘብ
- የውጭ ጉዳይ
- ያገር ግዛት
- ብዙ ጊዜ ጉትጉቼ ከ7—8 ወር ድረስ፤ ግን ለሚያስችኩል ብለው ስድስት ሚሊዮን ጠይቀን ተፈቅዶ፣ ጥር 65።

4/ አሜሪካኖች የምንጠይቀውን አምጡ አሉን።

- በኋላ (defenue) ያቀረበው 400 million
- ይህንን እሥራ ላይ ለማዋል በምን ያህል ገንዘብ ሚኒስቴር ጠየቀ። ማቅረብ አቃታቸው አንድ አንድ በማለኘት እናጠናዋለን።
- የጃንሆይ ሽዚት ደረሰ።
- ውጤት /የ73 ጉብኝት/

5/ ጉዳዩ በጣም ተጓተተ፤

- ሚኒመም ንገሩኝ በማለት ታሰፋ ጋራ ተነጋገርንበት፤
- ተጀነራል ከበደም፤

- ተምናሴ ለማም ጋር። (ሜጫ)

6/ እኔው ለመሄድ አስፈቀድኩ፤

- ቀጠሮ ተጠየቀ፤
- መልሱ ሳይመጣ ክራዚ ሆነ።

ነሐሴ 1966



ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ የሚያዝናናቸው ቢሾፍቱ ሆራ ሀይቅ ሄደው መዋኘት ነበር።

# Aklilu Remembers

Historical recollections from a prison cell
Aklilu Habtewold
Prime Minister of Ethiopia, 1961–1974

Translated by
Getachew Tedla

Addis Ababa University Press

# Contents

***"If by killing us you could redeem Ethiopia from poverty, we then accept your action as a blessing"***

Prime Minister *Tsehafe T'ezaz* Aklilu Habtewold's comment before being taken away to be shot to death on 24 November 1974, together with sixty other former officials of Emperor Haile Selassie's government.

(Recounted by *Ato* Ketema Yifru, *Mudaye*, First Year, No. 12, December 1992)

## Preface

This is a translation of the political autobiography of the late Prime Minister *Tsehafe T'ezaz* Aklilu Habtewold, which was submitted to the Commission of Inquiry that was appointed by the leaders of the 1974 revolution. The purpose of this translation is to make Aklilu's memoir accessible to historians, researchers, and other interested people.

The original Amharic manuscript entitled "*Report of Prime Minister Tsehafe T'ezaz Aklilu Habtewold, on the request of the Inquiry Commission*," was written on *Meskerem* 10, 1967 (September 17, 1974) while the late Prime Minister was in detention. The fifty-seven pages report is compartmentalized into seventeen major topics, with sub-headings. Tinted with foreign words and expressions (French and English) the report is a reflection of Aklilu's erudition. As the statement was written while the Prime Minister was in the Derg's prison, hence without a hold to reference documents, some of Aklilu's views relied on his memory span, at times put in a nutshell. (*Derg*, an Amharic term with literal meaning committee, is adapted to mean the Coordinating Committee of the Armed Forces that took over power from the government of Emperor Haile Selassie).

In order to help the reader, I have addressed the document in the following manner.

- Wherever I felt that some of the names or phrases written in foreign languages (e.g. French) are unclear, I translated it word by word and placed a question mark in square bracket [?].
- "*Janhoy*" which is repeatedly mentioned in the original document is an Amharic synonym for Emperor Haile Selassie. Throughout the document an English equivalent of the term, "The Emperor" is used.
- The late Prime Minister often referred to the USSR government as "Moscow" and its officials as "Moscobite"; I have chosen to use

the term "Soviet Union" to the country and "Russian" to the official.

- Due to ambivalence in the use of Amharic terms, the interpretation of certain words required a phrase or lines of sentences for a satisfactory explanation while others sufficed with just one word. Nevertheless, all the topics are translated line by line in accordance with the original document.

An Ethiopian name consists of the person's own name, followed by that of his father, unlike European names where the second name is a surname. Thus Ketema Yefru's and Yilma Deressa's own names are Ketema and Yilma, and their fathers' names are Yefru and Deressa. The patronymic helps to prevent confusion with namesakes. It is quite correct to refer them simply as Ketema and Yilma without any hint of familiarity, whereas it is a mistake to call them Mr. Yefru or Mr. Deressa as this creates confusion with their father's. Moreover, Ethiopian religious names are a compound of two words: Wolde Gabriel, for example, means Son of Saint Gabriel and Haile Selassie means Power of the Trinity. In general usage, such names are sometimes written as one word and sometimes as two. In this text such names are printed as one word. It is a mistake to use either part of such a name alone.

The Ethiopian New Year, *Meskerem* 1, falls on 11th September according to the Gregorian calendar, and the system of counting is between seven and eight years behind the Gregorian calendar. In the translated version wherever the Ethiopian calendar is used the Gregorian equivalent is mentioned in square brackets.

Pertinent introductory quotes from the book of the distinguished American Professor John H. Spencer's *ETHIOPIA AT BAY: A Personal Account of the Haile Selassie Years;* and Professor Christopher Clapham's book *HAILE SELASSIE'S GOVERNMENT* give readers a foresight into Aklilu's political life narrated herein. A chronological list of Aklilu's main appointments and activities, drawn by Professor John H. Spencer, is a marvellous illustration of the late Prime Minister's

commitment to national duty. A list of prominent Ethiopian personalities that are mentioned in the document is keyed at the end of the document.

To concentrate merely on the translation is limited to only background information.

I would like to take this opportunity to duly acknowledge the people who encouraged me to translate the authentic document. Very special thanks goes to my father, *Ato* Tedla Abebe, for providing me a copy of the document. Equally enormous thanks also goes to *Weyzero* Tersit Akalework who gave me beautiful pictures and valuable documents of the late Prime Minister, Aklilu Habtewold. I am very grateful to Professor Sven Rubenson for reading the first draft of the translation and for useful comments and suggestions he contributed. I am also indebted to Professor John H. Spencer for the details of Aklilu's career, which I have listed in the introduction. I sincerely extend my appreciation to Dr. Tadesse Zerihun who assisted me in translating, and gave me useful advice in finding the actual meaning and sense of the Amharic terminology.

Notwithstanding some difficulties in interpretation, I have attempted to the best of my ability to maintain the translation in direct correspondence with the original document.

I want to express my gratitude to Addis Ababa University Press and its employees for their professional support and finally for publishing the book.

Getachew Tedla (PhD)
Addis Ababa, Ethiopia

